## ምልከታ

በይርጋ ገብሬ ድሬታ (አዝማች)

ይህ ጉራጌ ቂጫ ጽሑፍ ለመጀመሪያ ጊዜ ትውፊቱን ወደ ጽሑፍ ሰነድነት ያሸጋገረ በመሆኑ ሂደቱ ታሪካዊ ነው:: በመጠኑም ቢሆን ስለክልሉና ስለዞኑ ተጨባጭ ሁኔታ ፈንጣቂ፣ ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥትና ከሃይማኖት ሥርዓቶች ጋር ተገናዛቢ ሆኖ መዘጋጀቱና ረቂቁ በተለያዩ በሣል ባለሙያች አስተያየት መዳበሩ ለጥናቱ አመርቂነት አስተዋጽኦ አድርጓል:: :: ከልደት እስከ ሞት፣ ከጋብቻ እስከ ፍቺ ያለውን ሥርዓት የቃኘ፣ ጠለፋን ሕገ-ወጥ አድርጎ መከላከያ ያበጀና የተጋቢዎችን መብት በእኩልነት ያረጋገጠ፣ ባጠቃላይ ለሕዝቡ ኤኮኖሚያዊና ማኅበራዊ ሕይወት ሥርዓት የዘረጋ፣ ከንብረት ማበላሸት፣ በአካል ላይ ጉዳት ከማድረስ እስከ ነፍስ መጥፋት ለሚከሰቱ ችግሮች የመዳኛ ሥርዓት ከነማስፈጸሚያው ያሰፈነ መሆኑ ደግሞ የሕዝቡ የራስ በራስ አስተዳደር ባህል ከፍተኛነትን ይጠቁማል::

ሕዝቡ ቋንቋውን ወደ ጽሑፍ ለማሸጋገር የወጠነውን ትልም ለማገዝ «የፊደል ገበታ» የቀረፀ፣ የማንነቱ መገለጫዎች ከሆኑት ነገሮች መሃል የሣምንት ቀናትና የወራት መጠሪያዎችን ያቀፈ፣ ከመቶ ላላነሱ የጉራጊኛ ቃላትና ሐረጎች ማብራሪያና ፍቺ ሰጥቶ ሰላሳ የሚጠጉ ዋቢ ሰነዶችን መዘርዘሩ የጉራጌን ማኅበራዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ባህላዊ ሕይወትን በደበልጥ ማወቅ ለሚሹ ወገኖች ምቹ ሁኔታን ፈጥሮአል:: የሰነዱ በአማርኛ መዘጋጀት ደግሞ ኢትዮጵያ የብዙ ብሔር፣ ብሔረሰቦችና ሕዝቦች አገር እንደመሆንዋ መጠን እያንዳንዱ ወገን በታሪክ ያፈራውን፣ በባህል የገነባውንና በዕድገት የሚጨብጠውን በጎ ነገር ሁሉ አደራጅቶ በማቅረብ ቀደም ሲል የተጀመረውን ብሔራዊ መስተጋብር ማጉልመስ የሚችሉ ልምዶችን ለመለዋወጥ ያግዛል::

ሰነዱ በአጠቃቀም ሂደት እየተፈተነ፣ በተገልጋዮች አስተያየት በመዳበር ከፍተኛ የእድገት ደረጃ የሚደርስ ይሆናል::

ዋጋ ብር 5.00 (አምስት ብር)

በንግድ ማተሚያ ድርጅት ታተመ



ጉሕራልድ-001/1991

# ጉራጌ ቂጫ



# KITCHA

## (The Guraghe Customary Law)

አዲስ አበባ
መስከረም 1991 ዓ.ም.



ጉሕራልድ-001/1991

# ኧጉራጌ ቂጬ



# KITCHA

## (The Guraghe Customary Law)

አዲስ አበባ
መስከረም 1991 ዓ.ም.

የሽፋን ዲዛይን ሃሳብ አመንጪ
ይርጋ ገብሬ ድረታ (አዝማች)
ሰዓሊ፣ ኃይሌ ሃብተየስ

ለመጀመሪያ ጊዜ መስከረም 1991 ዓ.ም. ታተመ

# ኧጉራጌ ቂጫ

## ማውጫ

ርዕሥ-ጉዳይ — ገጽ

ርዕሠ-ጉዳይ ገጽ







ርዕሠ-ጉዳይ

ገጽ

ርዕሠ-ጉዳይ ገጽ





ማውጫ

ርዕሠ-ጉዳይ ገጽ

ርዕሠ-ጉዳይ ገጽ







ርዕሠ-ጉዳይ ገጽ

# ኧጉራጌ ቈጫ

## 1. መቅድም

1.1 ቀደም ባሉና ዘመናዊ መንግሥታት ባልተመሠረቱባቸው ዘመናት በማንኛቸውም አገሮች ሕዝቦች ራሳቸውን የሚመሩባቸውና የሚያስተዳድሩባቸው ባህላዊና ልማዳዊ ሥርዓቶች እንደነበሩዋቸው የታሪክ ሰነዶች ይዘክራሉ/ ይመሠክራሉ:: አገሮች መንግሥት አቋቁመውና ሕገ-መንግሥት አውጥተው/ቀርፀው መመራት ከጀመሩባቸው ዘመናትና ዛሬም ቢሆን ባህላዊና ልማዳዊ የራስ በራስ አስተዳደር ሥርዓቶች በሕዝብ የዕለት ተዕለት ኑሮ ላይ የሚጫወቱትን አመርቂ ሚና ግንዛቤ ውስጥ በማስገባት ለባህላዊና ልማዳዊ የአስተዳደር ሥርዓቶች በሕገ- መንግሥቶቻቸው ጭምር ዕውቅና ይሰጣሉ:: ሥርዓቶቹም ለሕግ መስፈንና በቅርብ ሆኖ ለሕዝብ አገልግሎት በመስጠት የበኩላቸውን ሚና ይጫወታሉ::

1.2 በኢትዮጵያችንም ለልማዳዊና ለባሕላዊ የአስተዳደር ሥርዓቶች ዕውቅና የመስጠቱ ደረጃ ይለያይ እንጂ አገሪቱ የምትመራባቸው ሕገ-መንግሥቶች መቀረፅ ከጀመሩበት ወቅት አንስቶ እስከዛሬ ሕገ-መንግሥታቱ ለባሕላዊና ለልማዳዊ የአስተዳደር ሥርዓቶች ዕውቅና ሰጥተዋል:: እነዚህ ሁኔታዎች በ1948ቱ ዓ.ም. የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥትና በ1980ው ዓ.ም. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሕገ-መንግሥት በመጠኑ የተንፀባረቁ ሲሆኑ፣ በ1987 ዓ.ም. በወጣው የኢትዮጵያ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ ሕገ-መንግሥት ግን በግልጽ ተመልክቶአል:: ሕገ-መንግሥቱም ሁኔታውን እንደሚከተለው አስቀምጦታል::

> « *ይህ ሕገ-መንግሥት የግል እና የቤተሰብ ሕግን በተመለከተ በተከራካሪዎች ፈቃድ በሃይማኖቶች ወይም በባሕሉች ሕጎች መሠረት መዳኘትን አይከለክልም::*

*ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል።» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.34 ፣ ን.አ.5)*

*«መንግሥት መሠረታዊ መብቶችንና ሰብዓዊ ክብርን፣ ዴሞክራሲንና ሕገ-መንግሥቱን የማይቃረኑ ባሕሎችና ልማዶች በእኩልነት እንዲጎለብቱና እንዲያድጉ የመርዳት ኃላፊነት አለበት።»* *(መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.91፣ን.አ.1)*

1.3 የጉራጌ ሕዝብም እንደሌሎች ሕዝቦች ሁሉ ራሱን የሚመራበትና የሚያስተዳድርበት ባህላዊ፣፣ ልማዳዊና ሃይማኖታዊ ሥርዓት ነበረው፤ ዛሬም አለው። ሥርዓቱንም ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ጋር በተጣጣመ መልኩ ይጠቀምበታል። ይህ ራስን በራስ የመምራት፣ የማስተዳደርና የመዳኘት ሥርዓት ሕዝቡ በቋንቋው «እጉራጌ ቄጫ» በሚል ስያሜ ይጠራዋል፤ ያውቀዋል። ቄጫው የሕዝቡን ሕይወት ሁለንተና ዳሳሽ፣ ራስን በራስ የማስተዳደር የዳበረ ባህል መገለጫ፣ በራስ የመተማመን መሣሪያ እና ከትውልድ ወደ ትውልድ እየተሠራበት የተላለፈ አኩሪ ቅርስ በመሆኑ ሥልጣኔ ከወለደውና ከሚፈጥረው ጥበብ ጋር እያገናዘበ/እያጣጣመ ይጠቀምበታል፤ ይንከባከበዋል። «በቃል ያለ ይረሳል፤ በጽሑፍ ያለ ይወረሳል» እንዲሉ ቄጫውን ከቃል ትውፊትነት ወደ ጽሑፍ ሰነድነት ለመለወጥ በማሰብ የገጠሩ የሰባት ቤት ጉራጌ ሕዝብ እየተሰባሰበ ከ8 ዓመታት ላላነሰ ጊዜ ሲመክርበት ከቆየ በኋላ ሂደቱን በተማረ ሰው ኃይልና ሙያ ቅርፅ ለመስጠት እንዲቻል የጉራጌ ሕዝብ ራስ አገዝ ልማት ድርጅትን/ጉሕራልድን ድጋፍ ጠየቀ። የጉሕራልድ አመራርም ጥያቄውን ተቀብሎ በመተዳደሪያ ደንቡ መሠረት ሥራውን ማቀናጀት ጀመረ «የጉራጌ ኅብረተሰብ ታሪክና ባህል ተጠንቶ እንዲመዘገብና እንዲሠራጭ አስፈላጊውን ሁሉ ማድረግ።»





(የጉሕራልድ መተዳደሪያ ደንብ አንቀጽ 5፣ ንዑስ አንቀጽ 5.12)

1.4 ከተቀናጀ የቄጫው ጥናት ቀደም ብሎ በጉሕራልድ ደንብ አንቀጽ 5፣ ንዑስ አንቀጽ 5.12 በሰፈረው መሠረት የመላ ቤተ-ጉራጌ ታሪክና ባሕል ተጠንቶ እንዲመዘገብና እንዲሠራጭ አስፈላጊውን ሁሉ ለማድረግ በ1983 ዓ.ም. ከሁሉም ቤተ-ጉራጌ የተውጣጣ «የጉራጌ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ አጥኚና አማካሪ ግብረ-ኃይል» ተመሠረተ። ግብረ-ኃይሉም ተግባሩን በቅንጅት ለመከወን የሚያስችለው ድርጅታዊ አቋም አዋቅሮ ሊጠኑ የሚገባቸውን መስኮች ለይቶ የሚያሳይ ባለ 52 ገጽ ዝርዝር የጥናት ሰነድ አወጣ። ተጠኝ መስኮቹም፤

- ▷ → የክልሉ መልክዓ ምድርና የተፈጥሮ ሀብት
- ▷ → የጉራጌ ሕብረተሰብ አጠቃላይ ታሪክ /Socio-Political History
- ▷ → የሕብረተሰቡ ባህል
- ▷ → ማኅበራዊ ፋይዳዎች/Social Values
- ▷ → ልማዳዊ ሕክምና ፣ አካል ማሠልጠኛ፣ ስፖርት እና ኪነት
- ▷ → የቴክኖሎጂ ባህል
- ▷→ ባህላዊ አስተዳደርና ፍትሕ/ልማዳዊ ሕጎች/ Customary Administration & Law
- ▷→ የኅብረተሰቡ የዕድገት አቅጣጫዎችና የወደፊቱ አዝማሚያ፣ ወዘተ. ሊሆኑ እንደሚገባ ተመልክቶአል።

1.5 በእያንዳንዱ ርዕሰ-ጉዳይ ተካታች ዝርዝር ሁኔታዎችም በውል ተዘርዝረዋል። ሰነዱ ስለኅብረተሰቡ ቀደም ሲል የተጠኑ/የተጻፉ የጽሑፍ መረጃዎች፣ በጅምር ያሉ ሥራዎች የሚገኙበት ደረጃ ማመልከቻና የባለሙያዎች ዝርዝር ማጠናቀሪያ ቅጾችን በዕዝልነት አቅፎአል። ማስፈጸሚያ መዋቅሩ በአባሪነት የተያያዘ ሲሆን፣ በወቅቱ የተሳተፉ ክፍለ-ሕዝቦች የሚከተሉት ነበሩ፤

ዝርዝሩን ከመዋቅሩ ዕዝል ሦስት ላይ ይመለከተዋል:: እነርሱም፣

- ▷ → ስምንት ሰንጋ መስቃን
- ▷ → ሞኽር፣ አከሊልና መቆርቆር
- ▷→ ሥልጢኛ ተናጋሪ (ዳሎቻን፣ መልጋ ሣንኩራን፣ አዘርነት በርበሬን፣ ሥልጢን፣ አሊቾ ውሪሮን፣ ጦራ ላንፉሮን አካቶ)
- ▷ → ክስታኔ (ጉርደና ሶዶ)
- ▷ → ቸሃ
- ▷ → እንደገኝ
- ▷ → እኖርና ኤነር
- ▷ → ኧዣ
- ▷ → ወለኔ ገደባኖ
- ▷ → ጌታ
- ▷ → ጉማረ
- ▷ → ሰባት ጎጎት ዶቢ ነበሩ::

1.6 ሥራው በዚህ ሁኔታ እየተካሄደ እያለ የ1983ቱ የመንግሥት ለውጥ ሂደት ውስጥ ሲገባ ሌሎች በርካታ አጣዳፊ ክስተቶች በመፈጠራቸው ለጊዜውም ቢሆን እንቅስቃሴው ጋብ አለ:: የመንግሥት ለውጡ ሂደት እየሰከነ ሲመጣ ቀደም ሲል እንደተመለከተው በ1986 ዓ.ም. የሰባት ቤት ጉራጌ የገጠር አዛውንቶች በጉራጌ ቂጫ ጥናት የዕውቀትና የሙያ እገዛ እንዲደረግላቸው ጉሕራልድን ባሳሰቡት መሠረት የሥራው ውጥን ዳግም ተንቀሳቀሰ:: የአሁኑ ሥራ አትኩሮት ግን በጉራጌ ቂጫ ላይ ብቻ ነበር:: እንደ ቅድመ-ጥናት ሰነድ ዝግጅቱ ሁሉ ኧጉራጌ ቂጫን በመላው ቤተ-ጉራጌ ተሳትፎ ወደ ጽሑፍ ሰነድነት ለመለወጥ ቢሞከርም፣ ረቂቁ ጥናትም/ሰነድም ከተዘጋጀ በኋላ በወል አስተያየት ሰጥቶ ለማሟላት ጥረት ቢደረግም በሀገራችን በወቅቱ በየአካባቢው ይደረግ በነበረው የአስተዳደር አከላለል ሽግሽግ መንስዔ ተግባሩን ዕውን ማድረግ አላመቸም፤ በመሆኑም የቂጫው ጥናት በሰባት ቤት ጉራጌ አዛውንቶችና ምሁራን ብቻ ተጠናቀረ:: ነገር ግን፣ የጉራጌ ሕዝብ ካለው ቁርኝታዊ





የሥነልቦና፣ የባህል፣ የአኗኗርና የእምነት አንድነት ሳቢያ በአንዳንድ የቀበልኛ ቃላት አጠቃቀም ካልሆነ በቀር በመሠረታዊ የቂጫው ይዘት ልዩነት ይኖራል ተብሎ አይገመትም:: ሰነዱ በአማርኛ የተሰናዳ በመሆኑ ደግሞ የቀበልኛውም/የቋንቋውም አስቸጋሪነት በውል አይታይም:: አንዳንድ መቃናት የሚገባቸው ሁኔታዎች ቢኖሩ እንኳን ቂጫው እየተሠራበት በሂደት በጋራ ጥናት ወደፊት ሊስተካከሉ ይችላሉ::

1.7 የጥናቱ ተሳታፊዎች የጉዳዩ ባለቤት ከሆኑ የገጠርና የከተማ ነዋሪ አዛውንቶች፣ በተለያዩ መስኮች ዕውቀት ካላቸው በሳል ባለሙያዎች የተውጣጡ ናቸው:: (ዕዝል አንድን ይመለከተዋል::) ሰነዱ በረቂቅ ደረጃ ከተጠናቀቀ በኋላ በሕግ ባለሙያች፣ በኢኮኖሚስቶች፣ በማኅበራዊ ጉዳይ (ትምህርት፣ ጤና፣ ባህል፣ አካል ማሠልጠኛና ስፖርት) ፣ በባንክና በመድን ባለሙያዎች፣ በሣይኮሎጂስቶች፣ በሶሲዮሎጂስቶችና በአንትሮፖሎጂስቶች አስተያየት እንዲሰጥበት በመደረጉ እና የባለሙያ አስተያየቶቹም ለጉዳዩ ባለቤቶች ቀርበውላቸው በውይይት በአሁን ወቅት የሚፈልጉትንና የማይፈልጉትን ለይተው በማውጣታቸው ለሰነዱ ጥራት ከፍተኛ ዕገዛ አድርጉአል:: (ዕዝል ሁለትን ይመለከተዋል::)

1.8 ረቂቁ ኧጉራጌ ቂጫ ከተሠራጨ በኋላ ስድስት ኡላማዎች በ27-12-1988 ባረቀረቡት ሁለት ገጽ ማስታወሻና በግንባርም ተገኝተው ባብራሩበት ወቅት የሚከተለውን ሃሳብ ሰንዝረው ነበር:: «በእስልምና ሃይማኖት ሥርዓት መሠረት/በሸሪአ ሕግ መሠረት/በተጋቡ ወንድና ሴት መካከል የሚፈጠር የንብረት ሆነ የአስተዳደር ወይም ሌሎች በቂጫ ውስጥ የሚከሰቱ ሸሪአ-ነክ ችግሮች የሃይማኖት አባቶች/ ኡላማዎች በሚሰጡት መፍትሄ መሠረት ይፈጸም፤ ተብሎ በቂጫ ውስጥ መግባቱ አስፈላጊ ነው::» በውይይቱም ቂጫው የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ስለባህላዊ ሕጎች በደነገገውና በፈቀደው መሠረት ከሃይማኖትም ሆነ ከሌሎች ሕጎች ጋር

ተጣጥሞ የሚሄድና ሁለት ባለጉዳዮች በመረጡት ሥርዓት መተዳደርና መዳኘት እንደሚችሉ መግባባት ተደርሶአል:: ቺጫው ከሕግና ከማኅበራዊ ሥርዓቶች ጋር ተጣጥሞ እንደሚሠራበት በዚህ ሰነድ ዋና ይዘት ውስጥ በግልጽ ተመልክቶአል:: የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥትም ቀደም ሲል በተጠቀሰው አንቀጽ 34፣ ንኡስ አንቀጽ 5 እና በሌላም አንቀጽ እንደሚከተለው ደንግጎአል፤ ፈቅዶአል::

*«ሕገ-መንግሥቱ የሀገሪቱ የበላይ ሕግ ነው:: ማንኛውም ሕግ ልማዳዊ አሠራር እንዲሁም የመንግሥት አካል ወይም ባለሥልጣን ውሳኔ ከዚህ ሕገ-መንግሥት ጋር የሚቃረን ከሆነ ተፈጻሚነት አይኖረውም::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አንቀጽ 9፣ ንዑስ አንቀጽ 1)*

1.9 በቺጫ መሠረት የሚፈጸም ጋብቻ ሕገ-መንግሥታዊ ድጋፍ ያለው መሆኑ እንደሚከተለው ተመልክቶአል::

*«ብሕግ በተለይ በሚዘረዘረው መሠረት በሃይማኖት፣ በባሕል የሕግ ሥርዓቶች ላይ ተመስርተው ለሚፈጸሙ ጋብቻዎች እውቅና የሚሰጥ ሕግ ሊወጣ ይችላል::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.34፣ ን.አ.4)*

1.10 ጅጉራጌ ቺጫ የተጋቢዎችን መብት በእኩል የሚያይ ነው:: በቺጫው አንቀጽ 3፣ ንኡስ አንቀጽ 3.1 እና አንቀጽ 5.8 ላይ ቸግ (መተጫጨት) እና ጋብቻ በተጫጪዎችና በተጋቢዎች ሙሉ ፈቃደኝነት ላይ መመሥረት እንዳለበት ይደነግጋል:: ይህም ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ጋር በውል ተጣጥሞ የሚጓዝ ነው::

*«ጋብቻ በተጋቢዎች ነፃና ሙሉ ፈቃድ ላይ ብቻ ይመሠረታል::» (መስመሩ ለአፅንኦት*





*የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አንቀጽ 34፣ ን.አንቀጽ 2)*

1.11 ቺጫው ሴቶች በጋብቻ ውስጥ ከባሎቻቸው ጋር በጋራ ያፈሩትን ንብረት እኩል የመካፈልና ንብረት የማበጀት መብታቸውን በአንቀጽ 5፣ በንዑስ አንቀጾች ከ5.1 እስከ 5.5 ባለው ክፍሉ አረጋግጦአል:: ከጉዳ ባህሎችም እንዲጠበቁ በአንቀጽ 6 እና በሌሎችም ክፍሎች በማያሻማ መልኩ አስቀምጦአል:: የእነዚህም ሥርዓቶች ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ጋር ተዛማጅነታቸውና ተጣጣሚነታቸው በሕገ-መንግሥቱ እንደሚከተለው ተንፀባርቆአል::

*«ሴቶች ንብረት የማፍራት የማስተዳደር የመቆጣጠር የመጠቀምና የማስተላለፍ መብት አላቸው:: በተለይመሬትን በመጠቀም በማስተላለፍ በማስተዳደርና በመቆጣጠር ረገድ ከወንዶች ጋር እኩል መብት አላቸው እንዲሁም ውርስን በሚመለከት በእኩልነት የመታየት መብት አላቸው::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.35፣ ን.አንቀጽ 7)*

*«ሴቶች ከጎጂ ባህል ተጽዕኖ የመላቀቅ መብታቸውን መንግሥት ማስከበር አለበት:: ሴቶችን በአካላቸው ወይም በአዕምሮአቸው ላይ ጉዳት የሚያስከትሉ ሕጉች፣ ወጎችና ልምዶች የተከለከሉ ናቸው::» (ኤፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.35፣ ን.አ. 4)*

1.12 ቺጫው በወንጀል የተቀጣን ሰው መልሶ ከኅብረተሰቡ ጋር እንዲቀላቀል በማድረግ ረገድ ከወንጀለኛ መቅጫ የተለየ ባህርይ ይታይበታል:: አንድ በመንግሥት ሕግ (በወንጀለኛ መቅጫ) የተቀጣ ጥፋተኛ ቅጣቱን

ተጣጥሞ የሚሄድና ሁለት ባለጉዳዮች በመረጡት ሥርዓት መተዳደርና መዳኘት እንደሚችሉ መግባባት ተደርሶአል:: ቒጫው ከሕግና ከማኅበራዊ ሥርዓቶች ጋር ተጣጥሞ እንደሚሠራበት በዚህ ሰነድ ዋና ይዘት ውስጥ በግልጽ ተመልክቶአል:: የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥትም ቀደም ሲል በተጠቀሰው አንቀጽ 34፣ ንኡስ አንቀጽ 5 እና በሌላም አንቀጽ እንደሚከተለው ደንግጎአል፤ ፈቅዶአል::

> *«ሕገ-መንግሥቱ የሀገሪቱ የበላይ ሕግ ነው:: ማንኛውም ሕግ ልማዳዊ አሠራር እንዲሁም የመንግሥት አካል ወይም ባለሥልጣን ውሳኔ ከዚህ ሕገ-መንግሥት ጋር የሚቃረን ከሆነ ተፈጻሚነት አይኖረውም::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አንቀጽ 9፣ ንዑስ አንቀጽ 1)*

1.9 በቒጫ መሠረት የሚፈጸም ጋብቻ ሕገ-መንግሥታዊ ድጋፍ ያለው መሆኑ እንደሚከተለው ተመልክቶአል::

> *«ብሕግ በተለይ በሚዘረዘረው መሠረት በሃይማኖት፣ በባሕል የሕግ ሥርዓቶች ላይ ተመስርተው ለሚፈጸሙ ጋብቻዎች እውቅና የሚሰጥ ሕግ ሊወጣ ይችላል::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.34፣ ን.አ.4)*

1.10 ኧጉራጌ ቒጫ የተጋቢዎችን መብት በእኩል የሚያይ ነው:: በቒጫው አንቀጽ 3፣ ንኡስ አንቀጽ 3.1 እና አንቀጽ 5.8 ላይ ቸግ (መተጫጨት) እና ጋብቻ በተጫጪዎችና በተጋቢዎች ሙሉ ፈቃደኝነት ላይ መመሥረት እንዳለበት ይደነግጋል:: ይህም ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ጋር በውል ተጣጥሞ የሚጓዝ ነው::

> *«ጋብቻ በተጋቢዎች ነፃና ሙሉ ፈቃድ ላይ ብቻ ይመሠረታል::» (መስመሩ ለአፅንኦት*





> *የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አንቀጽ 34፣ ን.አንቀጽ 2)*

1.11 ቒጫው ሴቶች በጋብቻ ውስጥ ከባሎቻቸው ጋር በጋራ ያፈሩትን ንብረት እኩል የመካፈልና ንብረት የማበጀት መብታቸውን በአንቀጽ 5፣ በንዑስ አንቀጾች ከ5.1 እስከ 5.5 ባለው ክፍሉ አረጋግጦአል:: ከጉጂ ባህሎችም እንዲጠበቁ በአንቀጽ 6 እና በሌሎችም ክፍሎች በማያሻማ መልኩ አስቀምጦአል:: የእነዚህም ሥርዓቶች ከኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት ጋር ተዛማጅነታቸውና ተጣጣሚነታቸው በሕገ-መንግሥቱ እንደሚከተለው ተንፀባርቆአል::

> *«ሴቶች ንብረት የማፍራት የማስተዳደር የመቆጣጠር የመጠቀምና የማስተላለፍ መብት አላቸው:: በተለይመሬትን በመጠቀም በማስተላለፍ በማስተዳደርና በመቆጣጠር ረገድ ከወንዶች ጋር እኩል መብት አላቸው እንዲሁም ውርስን በሚመለከት በእኩልነት የመታየት መብት አላቸው::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.35፣ ን.አንቀጽ 7)*

> *«ሴቶች ከጎጂ ባህል ተጽዕኖ የመላቀቅ መብታቸውን መንግሥት ማስከበር አለበት:: ሴቶችን በአካላቸው ወይም በአዕምሮአቸው ላይ ጉዳት የሚያስከትሉ ሕጎች፣ ወጎችና ልምዶች የተከለከሉ ናቸው::» (ኤፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.35፣ ን.አ. 4)*

1.12 ቒጫው በወንጀል የተቀጣን ሰው መልሶ ከኅብረተሰቡ ጋር እንዲቀላቀል በማድረግ ረገድ ከወንጀለኛ መቅጫ የተለየ ባህርይ ይታይበታል:: አንድ በመንግሥት ሕግ (በወንጀለኛ መቅጫ) የተቀጣ ጥፋተኛ ቅጣቱን

ካጠናቀቀ በኋላ ከኅብረተሰቡ ጋር ለመቀላቀል በግሉ ከሚያደርገው ጥረት ሌላ በሕግ የተበጀለት ዘዴ/ሥርዓት ያለ አይመስልም:: እንጉራጌ ቈጫ ግን ባህላዊ ሥነ-ሥርዓት በተመላበት ስልት ቂም ቡቀል ተወግዶ ኅብረተሰቡ መግባባት በሰፈነበት ሁኔታ አብሮ መኖሩን የሚቀጥልበትን ሁኔታ ሁሉ ያመቻቻል:: ወንጀሉ ባጋጣሚ ከሕይወት መጥፋት ጋር የተያያዘ ቢሆን እንኳን ብቀላ በማይከሰትበት መልኩ መፍትሔ ያስገኝለታል::

1.13 እንጉራጌ ቈጫ ከአካል ማጉደል ጋር በተገናኘ የሚያስቀምጣቸው ማካካሻዎች ከዘመናዊ የመድን/የኢንሹራንስ ሥራ ጋር የተቀራራቢነት ባሕርይ ስለሚንፀባረቅበት የባህሉን የዕድገት ደረጃ ከፍተኛነትን ያመለክታል::

1.14 እንጉራጌ ቈጫ በአንቀጽ 25 ሕዝቡ የማንነቱ መገለጫና የባህሉ ነፀብራቅ በሆኑት «ቋንቋዎቹ» እንዲናገርና እንዲጽፍ ብሉም እንዲንከባከብና እንዲያሳድግ በዝርዝር ደንግጉአል:: ይህም ሕገ-መንግሥታዊ ድጋፍ ያለው በመሆኑ ለመተግበር ምቹ ሁኔታን ይፈጥራል::

> *«ማንኛውም የኢትዮጵያ ብሔር፣ ብሔረሰብ፣ ሕዝብ በቋንቋው የመናገር የመጻፍ ቋንቋውን የማሳደግ እና ባህሉን የመግለጽ፣ የማዳበርና የማስፋፋት እንዲሁም ታሪኩን የመንከባከብ መብት አለው::» (መስመሩ ለአፅንኦት የተጨመረ፣ ኢፌዲሪ ሕገ-መንግሥት አ.39፣ ን.አ.2)*

1.15 በ1970 ዓ.ም. የእናት አገር ጥሪ በዓል በሰባት ቤት ጉራጌ በተከበረበት ወቅት ለገቢ ማስገኛ ጭምር ተዘጋጅቶ በነበረ መጽሔት ውስጥ ለጉራጌ ቋንቋ ማሣደጉ የመጀመሪያ መሠረት የሚጥል እርሾ ሰፍሮአል:: ይኸውም የጉራጌ ቋንቋ ድምጾችን ወካይ





ሆሄያት በሳባ ፊደል ላይ ተመሥርቶ የጉራጊኛ ፊደል ገበታ መቀረጽ ነው:: የፊደል ቀረጻውም ከዕድገት በኅብረት የዕውቀትና የሥራ ዘመቻ ፕሮግራም የሚመነጭ ሲሆን፣ አዘጋጆቹ ፕሮፌሰር ኃብተማርያም ማርቆስና አዝማች ይርጋ ገብሬ ድረታ ናቸው:: ነፍሳቸውን ይማረውና ፕሮፌሰሩ በሕይወት ባይኖሩም ሥራቸው በጉራጌ ቅርስነት ከመቃብራቸው በላይ ይውላል:: የጉራጊኛ አነባበብ መፍቻው ከነአጠቃቀም ምሳሌው ለዋቢነት በዕዝል ቀርቦአል:: (ዕዝል አራትን ይመለከተዋል::)

1.16 ከሕዝቡ የዕለት ተዕለት መጠቀሚያ ቅርሶች መካከል ለአብነት የሣምንት ቀናት መጠሪያ ስሞችና የዘመን/የዓመት/የወር አቆጣጠር ሥርዓቶችም ዕዝል አምስትና ስድስት ላይ ተመልክተዋል::

1.17 በአንዳንድ ክፍለ-ሕዝቦች (ለምሣሌ በጌታ) መሥረቁ በውል የተረጋገጠበትና የተያዘ ሌባ ውሳኔ እስኪያገኝ ጠባቂ ተደርጐለት በተወሰነ ሥፍራ ይቆያል:: በዚህም ቆይታው የሚጠበቅበትን ቤት «ኪራይ»፣ የጠባቂውን «አበል»፣ የራሱንና የጠባቂውን ቀለብ እንዲችል ይደረጋል:: እርምጃውም ሌባውን በመጨረሻ ሊደርስበት ከሚችል ቅጣት የማያድነው ወይም የማይቀነስለት ተጨማሪ ዕዳ በመሆኑ ሌብነት እንዳይስፋፋ ተጽዕኖ ሊያደርግ እንደሚችል ይገመታል:: አሠራሩም ኅብረተሰቡን ከማያስፈልግ ወጪ ስለሚያድነው ትምህርታዊና ከፍተኛ የባህል ዕድገት ነፀብራቅ ነው::

1.18 ዕድርና ዕቁብ የመሳሰሉትን ማኅበራዊ መተጋገዣዎች መሥራች የሆነው የጉራጌ ሕዝብ ለኢትዮጵያ ግንባታ በኢኮኖሚው ዘርፍ ከሚያደርገው እንቅስቃሴ በተጨማሪ በሕዝቡ የዕለት ተዕለት ሕይወት ውስጥ ቁልፍ ሚና የሚጫወቱ የዕድርና የዕቁብ ሥርዓቶችን አበርክቶአል:: የራስ በራስ መተዳደሪያው/የቈጫው ከአፈ-ታሪክነት ወደ ጽሑፍ ሰነድነት መለወጥ ደግሞ ሌላው አንድ እርምጃ ወደፊት በመሆኑ ሌሎች ኢትዮጵያውያንም ባህላዊ የመተዳደሪያ ስርዓቶቻቸውን

መዝግበው/ ጽፈው በማሠራጨት ልምድ ለመለዋወጥ እንዲያደፋፍራቸው ይጠበቃል:: «ኢትዮጵያ የብዙ ብሔር፣ ብሔረሰቦችና ሕዝቦች አገር እንደመሆኑዋ መጠን የአገሪቱ ታሪክ፣ ባህልና ዕድገት የብሔሮችዋ፣ የብሔረሰቦችዋና የሕዝቦችዋ አጠቃላይ እንቅስቃሴ መስተጋብር ውጤት ነው ለማለት ይቻላል:: እያንዳንዱ ብሔር፣ ብሔረሰብና ሕዝብ በታሪክ ያፈራውን፣ በባህል የገነባውንና በዕድገት የሚጨብጠውን በጎ ነገር ሁሉ አደራጅቶ ቢያቀርብ ቀደም ሲል የተጀመረውን ብሔራዊ መስተጋብር እንደሚያጉለምስ ይታመናል::» (የጉራጌ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ አጥኚና አማካሪ ግብረ-ኃይል፣ ገጽ 2፣ አዲስ አበባ፣ ግንቦት 1983)

1.19 መቅድሙን ከመደምደም በፊት ስለቤተ-ጉራጌ መልክዓ-ምድር፣ የሕዝብ ቁጥርና የመሳሰሉ ጉዳዮች በመጠኑ መፈንጠቅ አግባብነት ስላለው የሚከተሉት ሁኔታዎች ተጠቋቁመዋል::

1.20 የዛሬው ቤተ-ጉራጌ ክልል ነዋሪ የነባር ሕዝብ፣ ከሰሜንና ከምሥራቅ የመጡ ወገኖች ድምር ውጤት እንደሆነ በዕዝልነት የተያያዙት ሰነዶች በዋቢነት ያመለክታሉ:: ታሪኩን ለታሪክ መዘክሮች በመተው ወደ ክልሉ ውሱን ፍንጠቃ ሽግግር ይደረጋል::

1.21 የጉራጌ ምድር የሚገኘው ከኢትዮጵያ ዋና ከተማ ከአዲስ አበባ ደቡብ-ምዕራብ 150-250 ኪሎ ሜትር እርቀት በቀድሞው ምዕራብ ሸዋ አስተዳደር፣ በዛሬው ጉራጌ ዞን (በደቡብ ኢትዮጵያ ብሔር፣ ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ክልል መስተዳድር) ነው:: ቀጥታ መገኛው በአማካኝ 37° 30Eና 38° 30E ሎንግቲዩድ እና 7° 30Nና 8° 30 N ላቲቲዩድ ሲሆን፣ የመሬት ከፍታው ከባህር ጠለል በላይ ከ1,000 እስከ 3,600 ሜትር ይደርሳል::

1.22 አቀማመጡ በኢትዮጵያ ከፍተኛ የዝናብ መጠን ከሚመዘገብባቸው ክለሎች አንዱ ሲሆን፣ አማካይ





ዓመታዊ የዝናብ መጠኑ ከ600 እስከ 1,600 ሚሊ ሜትር ሲደርስ ሙቀቱ ከ10°C እስከ 30°C ይሆናል:: የጉራጌ ወሰን በደቡብ ከሃድያና ከንባታ፣ በሰሜን ከጨቦ፣ በምሥራቅ ከአርሲ፣ በምዕራብ ደግሞ ከትልቁ ጊቤ/ዋቤ ወንዝ ይካለላል::

1.23 ሕዝቡ የሰፈረበት መሬት ስፋት 5,000 $km^2$ ሲሆን፣ በክለሉ ገጠርና ከተማዎች፣ ከክልሉ ውጪ በኢትዮጵያ የተለያዩ ክልሎች ሁሉ ተናኝቶ የሚገኘው ሕዝብ ቁጥር ከ3-5 ሚሊዮን እንደሚደርስ ሲገመት፣ ከዚህ ውስጥ ሁለት ሚሊዮኑ የሰባት ቤት ጉራጌ ሕዝብ ነው:: በአሁኑ መንግሥታዊ ያስተዳደር መዋቅር መሠረት የጉራጌ ዞን በ11 ወረዳዎች የተከፋፈለ ሲሆን፣ ቸሃ፣ ዳሎቻ፣ እዣና ወለኔ፣ ጎማረና ጌታ፣ እኖርና ኤነር፣ ጎሮ፣ ኮኪር፣ ላንፋሮ፣ መስቃንና ማረቆ፣ ሥልጢ እና ሶዶ በመባል ይጠራሉ::

1.24 አካባቢው በኢትዮጵያ ውስጥ ሕዝብ በጣም በተጨናነቀ ሁኔታ ከሚኖርባቸው ክልሎች አንዱ ሲሆን፣ በ$km^2$ ከ233-300 ሰዎች ይኖራሉ:: የዚህ የመሬት መጣበብ ደግሞ ከሕዝቡ መሃል በተለይ ወጣቱ ትውልድ ከቀየው እየወጣ ሥራና ትምህርት ፍለጋ በመላ ኢትዮጵያና በሌሎችም አገሮች እንዲናኝ ምክንያት ሆኖታል:: እ.ኤ.አ በ1974 ዓ.ም. የኢትዮጵያ ምግብ ጥናት ተቋም (ENI) በሰባት ቤት ጉራጌ ባካሄደው ጥናት ሥራ ፍለጋ ከቀያቸው ወጥተው በያለበት የሚሰማሩ ወጣት ወንዶች ቁጥር በመቶ ሲሰላ ከ96.2% እስከ 99.5% እንደሚደርስ አመልክቶ ነበር:: አሁን ባለው ሁኔታ ሲቃኝ ደግሞ የፆታ ስብጥሩ ሁለቱንም ጾታዎች የሚያካትት ሲሆን፣ ከዚያን ወዲህ ጥናት ባለመደረጉ ነው እንጂ ሥራ ፍለጋ የትውልድ ቦታቸውን ጥለው የሚወጡ ወጣቶች ቁጥር መቶኛ ከፍ እንደሚል ከተጨባጩ ሁኔታ መገንዘብ ይቻላል::

1.25 ወጣቱ በሥፋት ሥራ ፍለጋም ሆነ ለትምህርት ከቀየው ቢፈልስም ባለው ከፍተኛ የቤተሰብ ቁርኝታዊ

ግንኙነትና ማኅበራዊ ትስስር ሳቢያ የእርሻና የቤት መሥሪያ ወቅታትን ታላላቅ ብሔራዊና ባህላዊ በአላትን፣ የደስታና የሃዘን አጋጣሚዎችን ወዘተ.. በማስታከክ ወደ ትውልድ ቦታውና ቤተዘመድ ይመላለሳል:: በሄደበት ሥፍራ ትዳር መሥርቶና ንብረት አፍርቶ የሚኖር እንኳን ቢሆን ከፍ ብሎ በተጠቀቆሙ ምክንያቶች ወደ ትውልድ ቀየውና ዘመዶቹ ከመመላለስ አያግዱትም:: በገጠር ነዋሪ የሆኑ አዛውንቶችም ቢሆኑ ገንዘብ የሚጠይቁ መንግሥታዊና ማኅበራዊ ኃላፊነቶቻቸውንና ግዴታዎቻቸውን ለመወጣት እንዲያስችላቸው፣ እንዲሁም ለደስታና ለሃዘን አጋጣሚዎች ልጆቻቸውና ዘመዶቻቸው ለሥራም ሆነ ለትምህርት ወደ ተሰማሩባቸው ሥፍራዎች መመላለሱ ያልተለመደ አይደለም:: አብዛኛው ሰው በንግድ ሥራ ዘርፍ የመሰማራት ጠባይ ስለሚታይበት በሥራው ባህርይ ምክንያት ተመላላሽ ነው:: የጤናና የትምህርት ተቋማት አለመሟላትም አገልግሎቶችን ለማግኘት ከአካባቢው ለመውጣት ሌላ ምክንያት ሆኖታል:: እ.አ.አ. በ1984 የስታቲስቲክስ ባለሥልጣን ባካሄደው የሕዝብና የቤት ቆጠራ አዲስ አበባ ውስጥ ይኖር ከነበረው 1,309,320 ሕዝብ ከሩብ ሚሊዮን በላይ (255,132) የጉራጌ ብሔረሰብ እንደነበረና መቶኛውም 18% ሲሆን፣ በብዛት በሁለተኛ ደረጃ መገኘቱ የሕዝቡን በየቦታ መኖር ሌላው ዋቢ ነው:: ከፍ ብሎ የተመለከቱ ሁኔታዎች የጉራጌን ሕዝብ በተከታታይ ተንቀሳቃሽ እንዲሆን አድርገውታል::

1.26 ይህን በሁኔታዎች አለመመቻቸት ምክንያት የተፈጠረውን የተንቀሳቃሽነት ባህርይ ፍላጎት ለማሟላት የጉራጌ ሕዝብ የራስ አገዝ ልማት መሥርቶ አካባቢውን ለማልማትና በመነሻነትም መንገድ ለመሥራት በ1936ና በ1937 ዓ.ም. እንቅስቃሴ ቢጀመርም በተለያዩ ምክንያቶች ሳይሳካ ቀየ:: ተስፋ ባለመቁረጥ በገጠርና በከተማ እንደገና በ1941ና በ1942 ዓ.ም. ሕዝቦቹ ዳግም የልማት እንቅስቃሴ ወጠኑ፤ ያኔም ቢሆን ጥረቱ ለውጤት አልበቃም:: ሕዝቡ ለልማት ቆርጠ የተነሳ በመሆኑ እንቅፋቶች ሳያግዱት





ለሦስተኛ ጊዜ በ1953 ዓ.ም. በተጠናከረ ሁኔታ ጥረቱ ቀጠለ:: በሂደቱም ሁለት አንጋፋ የመንገድ ሥራ ድርጅቶች ተወለዱ:: ይኸውም የጉራጌ ክፍለ ሀገር መንገዶች ሥራ ድርጅት ኮሚቴ በሰኔ ወር 1954 ዓ.ም. ሲመሠረት፣ በ1955 ዓ.ም. ደግሞ ከዓለም ገና ወላሞ ሶዶ የመንገድ ሥራ ድርጅት ተቋቋመ:: ሁለቱ ድርጅቶች በየበኩላቸው የሕዝቡንና የመንግሥትን ጥረት በማስተባበር የክልሉን ሶሲዮ-ኤኮኖሚ ይዘት ለማሻሻል የተቻላቸውን ሁሉ አድርገዋል፤ አመርቂ ውጤቶችንም አስመዝግበዋል:: የሕዝቡንም የራስ-አገዝ ልማት ተምሳሌትነት አስመስክረዋል:: ከነዚህም ድርጅቶች ገጠመኝና ተመክሮ በመነሳት ዛሬ አሥራ ሰባቱም ቤተ-ጉራጌዎች የየራሳቸው የልማት ድርጅት/ማኅበር አቋቁመው በልማትና በማኅበራዊ አገልግሎት ግንባር ቀደም ሚና እየተጫወቱ ነው::

1.27 የቂጫው ጥናት ስብሰባዎች የተካሄዱት በአገር ቤት በተለያዩ ሥፍራዎችና አልፎ አልፎ በአዲስ አበባ ነው:: የጥናቱ የተወሰኑ ክፍሎች ሲጠናቀቁ በሕዝብ ጠቅላላ ጉባዔ እየተመረመሩ እንዲፀድቁ ተደርጐአል:: ለቂጫው ዝግጅት ከአዲስ አበባ ወደ አገር ቤት፣ ከአገር ቤት ወደ አዲስ አበባ የተደረጉ ጉዞዎች ያስከተሉት ወጪና ማሣተሚያውን የሸፈነው የጉራጌ ሕዝብ ራስ አገዝ ልማት ድርጅት ነው:: ይህ ቂጫ እንደማንኛውም የሕዝብ መተዳደሪያ ሥርዓት/ደንብ/ሕግ ወቅቱን ጠብቆ ሊሻሻል የሚችል ይሆናል:: ለሥራው መቃናት ክረምትና በጋ ወይም የቦታ እርቀት ሳያግዳቸው አመርቂ ተሳትፎ ላደረጉና ሁኔታዎችን ከማመቻቸትና ሥራውን አቀናብሮ ከመምራት በተጨማሪ አስፈላጊውን ወጪ ሁሉ ለሸፈነው ጉሕራልድ በሕዝቡ ስም ልባዊ ምስጋና እናቀርባለን::

ይርጋ ገብሬ ድረታ (አዝማች)
የጉሕራልድ ፕሬዚዳንት፣ የቂጫው
ጥናት ሊቀመንበር፣ የሰነዱ አቀናጅና ኤዲተር

## 2. 2.1 የቺጫው አዘገጃጀት ሂደት

2.1.1 የቤተ-ጉራጌ ሕዝብ ለረዥም ዘመናት የራሱ የሆነ ባህላዊ የአስተዳደርና የፍትሕ ሥርዓት ደንግጎ ሲሠራበት ኖሮአል፣ እየሠራበትም ነው። ባሕላዊ የአስተዳደርና የፍትሕ ሥርዓቶቹ ከአንድ ትውልድ ወደተከታዩ ትውልድ ተሸጋግረው ዛሬ ወደ አለንበት ዘመን የደረሱት በሰነድ መልክ ተጽፈው ሳይሆን በቃል ብቻ ከወላጆች ወደልጆች ሲተላለፉና ሲሠራባቸው ቆይተው ነው። በየጊዜው ማሻሻያዎችና ተጨማሪ ሴራዎች ሲያስፈልጉም ባህላዊ ሸንጎ ተወያይቶባቸውና አጽድቆአቸው እንደተለመደው በቃል እየተነገሩ ሲተገበሩ እንደነበር ይታወቃል። በ1962 ዓ.ም. የሰባት ቤት ጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ ያሻሻላቸው ጥቂት ባህላዊ ያስተዳደር ሥርዓቶች በቀኛዝማች ኃይሌ ገብረመስቀል በማስታወሻ መልክ በጽሑፍ ተይዘው ተገኝተዋል። ሆኖም ማስታወሻው በሰነድነት የታወቀ አልነበረም። በ1983 ዓ.ም. የቤተ-ጉራጌ ታሪክና ባህል ማጥኛ መመሪያ ሰነድ በጉሕራልድ አቀናጅነት በመላ ቤተ-ጉራጌ አባላት ተሳትፎ ቢዘጋጅም ሊጠኑ የገሚባቸው ሤራዎችን ስም ይጠቅሳል እንጂ ዝርዝር ጉዳይ ውስጥ አይገባም።

2.1.2 ሲሠራባቸው የነበሩትን ሤራዎች ለማሻሻልና ከጊዜው ሂደት ጋር የተገናዘቡ ሌሎች ዝርዝር ሤራዎችንም አጥንቶ ለመደንገግና በሰነድነት እንዲያዙ ለማድረግ የሰባት ቤት ጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ ለስምንት ዓመታት ያህል ብርቱ ጥረት አድርጎአል። ከከተማ ነዋሪ ተወላጆችም እነ ክቡር ሌ/ጄኔራል ወልደሥላሴ በረካና ሌሎችም ከአዲስ አበባ አገር ቤት ድረስ በመመላለስ በምክሩ ተሳትፈዋል። ሆኖም በልዩ ልዩ ምክንያት ባህላዊ ሸንጎው ፍጻሜ ላይ መድረስ ችግር ስለገጠመው በከተማ ነዋሪ የሆኑ ተወላጅ ሽማግሌዎችና ምሁራን በጥናቱ በስፋት





እንዲሳተፉ ጥያቄ አቀረበ። እንደዚሁም ባህላዊ ሸንጎው እቅዱን ማሳካት እንዲችል የራሱ የሆነውን የጉራጌ ሕዝብ ራስ አገዝ ልማት ድርጅትን (ጉሕራልድን) ድጋፍ ጠየቀ። ጉሕራልድም ከተግባሮቹ አንዱ የጉራጌ ሕዝብ ታሪክና ባህል ጥናት እንዲካሄድ ማድረግ ወይም መርዳት ስለሆነ ጥያቄውን በመቀበል ከሰባቱም ክፍለ-ሕዝቦችና ከጉሕራልድ ዋና መሥሪያ ቤት የቺጫ ጥናትን በማካሄድ ይረዳሉ ወይም ይጠቅማሉ፣ ያውቃሉ ተብሎ የታመነባቸውን አባላት መርጠው እንዲያስታውቁ ተደረገ። የተመረጡት አባላትም በባህላዊ ሸንጎ ስብሰባዎች በተሳታፊነት እንዲገኙ መመሪያ ተሰጠ። ጉሕራልድም በመተዳደሪያ ደንቡ መሠረት ለጥናቱ አስፈላጊ የሆኑ እገዛዎች ማድረጉን ቀጠለ።

2.1.3 ባሕላዊ ሸንጎው የካቲት 19 ቀን 1986 ዓ.ም. በቸሃ ወረዳ በእምድብር አንደኛና መለስተኛ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ቅጥር ግቢ ውስጥ ጠቅላላ ጉባዔ አካሄደ። በባህላዊ ሸንጎው ስብሰባም የሰባት ቤት ጉራጌ የቺጫ ሽማግሌዎች፣ ከየክፍለ-ሕዝቡና ከአዲስ አበባ የተወከሉ አባላት ተገኝተዋል። የዚህ ጠቅላላ ባሕላዊ ሸንጎ ዋና ዋና አጀንዳዎችም ፣

▷ → ሲሠራባቸው ያሉ ሤራዎችን ገምግሞ ማሻሻል፣ በተለይም አጣዳፊ ለሆኑት ቅድሚያ በመስጠት፣ መወሰን፣

▷ → ተጨማሪ ሤራዎችን መደንገግ፣

▷ → ሤራዎቹ በሰነድ ሊሠፍሩ የሚቻልበትን መንገድ መፈለግና ሁኔታዎችን ማመቻቸት፣

- ▷ → የቺጫ ሰነዱም ታትሞ ለተጠቃሚው ሕዝብ በስፊው የሚዳረስበትን መንገድ መሻትና ፍጻሜ እንዲያገኝ ማድረግ፣

- ▷ → ለዚህ ሥራም ከአገር ቤትና ከአዲስ አበባ የተውጣጣ ኮሚቴ ማቋቋም ነበሩ::

2.1.4 ባህላዊ ሸንጎው በአጀንዳው ቁጥር አንድ መሠረት በጣም አንገብጋቢ የነበሩትን፣

- ▷ → ከግድያ
- ▷ → ከቤት ቃጠሎና
- ▷ → ከጋብቻ ጋር የተያዙ ሴራዎች ላይ ጠቅለል ያሉ የማሻሻያ ውሳኔዎችን አሳልፎ ሌሎች ማሻሻያዎችና ተጨማሪ ሄራዎችን እያጠና የውሳኔ ሃሳብ ለጠቅላላው ባህላዊ ሸንጎ እንዲያቀርብ ከአገር ቤትና ከአዲስ አበባ የተውጣጣ የቺጫ አጥኚ ኮሚቴ አቋቋመ::

2.1.5 ኮሚቴውም መጋቢት 10 ቀን 1986 ዓ.ም. ጠቅላላ ባሕላዊ ሸንጎው የካቲት 19 ቀን 1986 ዓ.ም. በተሰበሰበበት ሥፍራ ተገኝቶ ከጠቅላላ ባሕላዊ ሸንጎው በተሰጠው መርሐ-ግብር መሠረት ሥራውን ጀመረ:: አጀንዳዎቹም ፣

- ▷ → በ19-06-1986 ባሕላዊ ሸንጎው የወሰናቸውን ሄራዎች በጊዜያዊ ሰነድነት የተወሰነ ሥርጭት እንዲጀመር ማድረግ፣

- ▷ → በቺጫ ጥናቱ አካሄድ ላይ ተወያይቶ ሃሳቦችን መንደፍ፣

- ▷ → ስለሚጠኑ ሄራዎች ጠቅለል ባለ መልኩ ዝርዝር ማጠናቀር፣





- ▷ → ቅድሚያ የሚሰጣቸውን ሄራዎች መርጦ ማስቀደም፣

- ▷ → ቅድሚያ በተሰጣቸው ሄራዎች ላይ ተወያይቶና ገምግሞ የውሳኔ ሐሳብ ለግንቦት 6 ቀን 1986 ዓ.ም. ጠቅላላ ባሕላዊ ሸንጎ ለማቅረብ መዘጋጀት፣

- ▷ → የተሻሻሉና እንዲሻሻሉ የውሳኔ ሃሳብ የሚቀርብላቸው ሄራዎች ማስፈጸሚያ ሥርዓትን መንደፍ ነበሩ::

2.1.6 በዚሁ መሠረት ኮሚቴው ሚያዝያ 1 ቀን 1986 ዓ.ም.፣ ሚያዝያ 2 ቀን 1986 ዓ.ም. እና ሚያዝያ 6 ቀን 1986 ዓ.ም. በጉሕራልድ ዋና መሥሪያ ቤት አዲስ አበባ፣ እንደዚሁም ግንቦት 6 ቀን 1986 ዓ.ም. በእምድብር መለስተኛ 2ኛ ደረጃ ት/ቤት ተሰብስቦ ግድያን፣ አካል ማጉደልን፣ ጋብቻን፣ አልኮሆል መጠጥና ጉጂ ዕጾችን፣ የቤት ቃጠሎንና የቺጫ አስፈጻሚ አካልን ያካተተ የመጀመሪያው ከፊል የቺጫ ጽሁፍ በሰነድነት አዘጋጅቶ ለጠቅላላ ባህላዊ ሸንጎ አቀረበ:: ጠቅላላ ባሕላዊ ሸንጎውም ከኮሚቴው የቀረበለትን የውኔ ሃሳብ መርምሮ ከግንቦት 6 ቀን 1986 ዓ.ም. ጀምሮ ሌላው ተጠናቅቆ እስከሚያልቅ ድረስ ሳይጠብቅ በጊዜአዊነት ተፈጻሚ እንዲሆንና ሰነዱም እንዲሠራጭ ወሰነ:: ይህም የመጀመሪያው ውስንና ጊዜያዊ የቺጫ ሰነድ ሆነ::

2.1.7 ኮሚቴው ጥናቱን ቀጥሎ ሰኔ 10፣ 11 እና 12 ቀን 1986 ዓ.ም. በጉሕራልድ ዋና መሥሪያ ቤት አዲስ አበባ፣ ሐምሌ 2 ቀን 1986 ዓ.ም. በእምድብር መለስተኛ 2ኛ ደረጃ ት/ቤት ተሰብስቦ ክፍል 2 የቺጫ የውሳኔ ሐሳብ የያዘ ሰነድ አቀረበ:: ባሕላዊ ጠቅላላ ሸንጎውም ሐምሌ 3

ቀን 1986 ዓ.ም. ከዚህ በላይ በተጠቀሰው ት/ቤት ቅጥር ግቢ ተሰብስቦ በቀረበው የቺጫ የውሳኔ ሃሳብ ላይ ሰፊ ውይይት አድርጎ አንዳንድ ማሻሻያዎችን በማከል ከንግቦት 6 ቀን 1986 ዓ.ም. ጀምሮ እንዲሠራባቸው ስተወሰኑ ሜራዎች በተጨማሪ በጊዜአዊነት እንዲተገበሩ ወስኖ ሰነዱም እንዲሠራጭ አዘዘ::

2.1.8 አጥኚው ኮሚቴ ሥራውን በመቀጠል ሐምሌ 23 እና 24 ቀን 1986 በወልቂጤ ጉሕራልድ ትራንስፖርት ዘርፍ ጽ/ቤት፣ መስከረም 6 እና 7 ቀን 1987 አዲስ አበባ ጉሕራልድ ዋና መሥሪያ ቤት ባደረጋቸው ስብሰባዎች ክፍል ሦስት ተጨማሪ ሜራዎችን የያዘ ሰነድ መርምሮ በማጽደቅ ለጠቅላላው ባሕላዊ ሸንጎ እስከሚቀርብ ድረስ ሳይጠበቅ በክፍል አንድና ሁለት ከጸደቁት ሜራዎች ጋር በሥራ ላይ እንዲውልና በሚቀጥለው ስብሰባ ለሸንጎው ሪፖርት እንዲደረግና ሰነዱም እንዲሠራጭ ወሰነ:: ቺጫውን ለኅብረተሰቡ በዝርዝር ለማስተዋወቅና ለማስረዳት በሰባቱም ክፍለ - ሕዝቦችና በአበሽጌ ገለጻ ለማድረግ ታቅዶ በወቅቱ በነበሩ ሁኔታዎች ምክንያት ፕሮግራሙ ተግባራዊ ባይሆንም የኮሚቴው ጥናት ቀጥሎ ቀደም ሲል ኮሚቴው ያቋቋማቸው የጤና፣ የትምህርትና የሥነ-ሕዝብ፣ የሕግ፣ የኤኮኖሚ ጉዳዮች፣ የማህበራዊ ጉዳዮች ግብረ-ኃይሎች ያቀረቧቸው ሙያዊ አስተያየቶችና የውሳኔ ሐሳቦችን በሚመለከት ዝርዝር ውይይት ተደረገ:: የሙያ በሚመለከት ዝርዝር ውይይት ተደረገ:: የሙያ ግብረ-ኃይሎቹ ብዙ ጠቃሚና ገንቢ ሃሳቦችና ማሻሻያዎችን አቅርበዋል::

2.1.9 የጥናት ቡድኑ ጥቅምት 19 እና 20 ቀን 1987 ተሰብስቦ በክፍል አንድ፣ ሁለትና ሦስት በጊዜአዊነት እንዲሠራባቸው ከተወሰኑት ሜራዎች አንዳንዶቹን ከባለሙያዎች በቀረቡ ሃሳቦች መሠረት በማሻሻልና አዲስ ሜራዎችንም





በመጨመር ክፍል አራት የቺጫ የውሳኔ ሃሳብ ለባሕላዊ ጠቅላላ ሸንጎ አቀረበ:: ባህላዊ ጠቅላላ ሸንጎውም በክፍል ሦስት በኮሚቴው እንዲተገበር የተደረገውንና በክፍል አራት የቀረቡ ማሻሻያዎችና ተጨማሪ ሜራዎችን መርምሮ አጸደቀ:: ከክፍል 1-4 ተጠንተው ቀርበው በባህላዊ ሸንጎው የፀደቁ ሜራዎች ተጠቃልለውና ታትመው በሰነድነት ለሕዝቡ እንዲሠራጭ ወሰነ :: ገና ያልተጠናቀቁና የሚሻሻሉ ሜራዎች እንዳሉም የታወቀ ስለሆነ አሁን በፀደቁት እየተሠራ ጥናቱ መቀጠል እንዳለበት ተወስኖአል::

2.1.10 የካሣ ክፍያ መጠንን በሚመለከት ብዙ ያከራከሩ ሜራዎች ቢኖሩም ከሁሉም በላይ አሳሳቢነቱ በባለሙያዎችና በአንዳንድ ሽማግሌዎች የተገለጸው የነፍስ ግድያ ሜራ ካሣ መጠን ነው፤ ማለት ብር 30,000 /ሠላሣ ሺህ ብር/ በግፍ ለተገደለ ሰው ሕይወት በጣም አነስተኛ ስለሆነ ከብር 30,000 - 120,000 ከፍ ማለት እንደሚገባ ሐሳብ ቢቀርብም ለአሁኑ በዚሁ በብር 30,000 (ሠላሣ ሺህ ብር) ተወስኖ ለወደፊት በሚሻሻል ጊዜ ይታያል በሚል ታልፎአል::

2.1.11 ከዚህ በላይ የተጠቀሱት ባህላዊ ጠቅላላ ሸንጐዎችና የቺጫ አጥኚ ኮሚቴ ስብሰባዎች የተመሩት በአዝማች ይርጋ ገብሬ ድረታ ዋና ሊቀመንበርነትና በዋይደማም ዘርፉ አንሣ ተባባሪ ስብሳቢነት እና በአቶ ወልደማርያም ወልደሚካኤል ፀሐፊነት ነው:: የስብሰባዎች ሁሉ ውይይቶችና ውሳኔዎች ቃለ ጉባዔዎች በፀሐፊው ተመዝግበው በአባላት የተፈረመባቸው ሲሆን፣ ውሳኔዎቹ የመነጨትና የተጠናቀሩት ከእነዚሁ መሠረታዊ ሰነዶች ነው::

2.1.12 ይህ የቺጫ ሰነድ መቅድሙን፣ መግቢያውን፣ የአጥኚዎችንና የአስተያየት ሰጪ ባለሙያዎችን

ዝርዝር፣ ዕዝሎችንና የዋቢ ሰነዶችን ዝርዝር ሳይጨምር በአሥራ ስድስት ምዕራፎች፣ በአርባ ሦስት አንቀጾች እና በበርካታ ንዑስ አንቀጾች ተከፋፍሎ የቀረበ ነው:: በዚሁ መሠረት ምዕራፍ አንድ ጠቅላላ፣ ምዕራፍ ሁለት ጋብቻና ተዛማጅ ጉዳዮችን፣ ምዕራፍ ሦስት ሐዘንና ተዝካርን፣ ምዕራፍ አራት ኢኮኖሚና ማኅበራዊ ጉዳዮችን፣ ምዕራፍ አምስት የቤት አሠራር፣ የጀፎረ፣ የቂየ፣ የሞጣ፣ የባህላዊና የሰረጌ ቦታዎች አጠቃቀምን፣ ምዕራፍ ስድስት የባህላዊ ሕክምና፣ አካል ማሠልጠኛ፣ ስፖርትና ኪነትን፣ ምዕራፍ ሰባት ንብረትን፣ ምዕራፍ ስምንት ሥርቆትን፣ ምዕራፍ ዘጠኝ አልኮሆል መጠጥ ጉጂ ዕጾችን፣ ምዕራፍ አሥር አካል ማጉደልን፣ ምዕራፍ አሥራ አንድ ግድያን፣ ምዕራፍ አሥራ ሁለት በቋንቋ መጠቀምን፣ ምዕራፍ አሥራ ሦስት ኽቄጫ ማስፈጸሚያ ተጓዳኝ ሁኔታዎችን፣ ምዕራፍ አሥራ አራት ያፈጻጸም ተዋረድን፣ ያስፈጻሚ ምርጫንና ስብሰባዎችን፣ ምዕራፍ አሥራ አምስት ልዩ ልዩ ድንጋጌዎችን፣ ምዕራፍ አሥራ ስድስት ደግሞ ድምዳሜን ይዘው ቀርበዋል::

ወልደማርም ወልደሚካኤል
የጉሕራልድ ቀ/ም/ፕሬዚዳንት
የአጥኚው ኮሚቴ ፀሐፊና
ከቃለጉባዔ መነሻ ነጥቦችን አጠናቃሪ



# ኽጉራጌ ቄጫ

## ምዕራፍ አንድ

<u>ጠቅላላ</u>

(ከቃል ወደ ጽሑፍ ሰነድ ተሸጋጋሪነትና ትርጓሜ)

### አንቀጽ አንድ

1. <u>የቄጫው ከቃል ወደ ጽሑፍ ሰነድ ተሸጋጋሪነት</u>

በመላ ቤተ-ጉራጌ ተነሳሽነትና በተወሰኑ ክፍለ-ሕዝቦች ተጨባጭ እርምጃ ወሳጅነት ኽጉራጌ ቄጫ ከቃል ወደ ጽሑፍ ሰነድነት እንዲሸጋገር ተደርጕአል:: የሰነዱም መለያ ጉሕራልድ. ቄጫ.001/1991 ተብሎ ሊጠቀስ ይችላል::

### አንቀጽ ሁለት

2. <u>ትርጓሜ/ማብራሪያ/ፍቺ</u>

2.0 የቃሉ/የሐረጉ አገባብ ሌላ ትርጉም እንዲሰጠው ካላስፈለገ በቀር በዚህ ቄጫ ውስጥ የሚከተሉት ቃላትና ሐረጎች ትርጓሜ /ፍቺ/ ማብራሪያ ቀጥሎ እንደተመለከተው ይሆናል::

2.1 <u>ቄጫ፣</u>

ሕገ-ቤተጉራጌ፣የጉራጌ ባህላዊ ሕግ፣ ያስተዳደርና ፍትሕ ሥርዓት

2.2 <u>ሜራ፣</u>

ደንብ፣ ሕግ፣ ሥነ-ሥርዓት

## 2.3 ኽ፣

በአንዳንድ የጉራጌ ቋንቋ (ለምሳሌ በጜቲና፣በእኖሪና፣ በኤነሪና እና በእንደገኚና) የአማርኛውን «የ» ሆሄ ሊወክል/ሊተካ የሚችል የጉራጊኛ ሆሄ ነው። ለምሳሌ «ኽጉራጌ ቂጫ» ሲል የጉራጌ ቂጫ ማለት ነው። በአነባበብ ወቅት ከአማርኛው «የ» ሆሄ ጋር እየተመሳሰለ እንዳያስቸግር በቂጫው ውስጥ ቃሉ ጉራጊኛ በሚሆንበት ጊዜ በ«የ» ፈንታ ለግልፀት ሲባል «ኽ» ግልጋሎት ላይ እንዲውል ተደርጉአል።

## 2.4 ኽጉንደር ንጉሥ/አዝማች

ባህላዊ መሪ፣ አስተዳዳሪና ዳኛ ማለት ነው። ቀደም ሲል እያንዳንዱ ጉሣ ራሱን በራሱ ያስተዳድር በነበረ ወቅት አንዳንዱ ጉሣ «ኽጉንደር ንጉሥ» የሚባል ባህላዊ መሪ፣ አስተዳዳሪና ዳኛ ነበረው። መሪውም ከትውልድ ወደ ትውልድ የሚተላለፍ የኃላፊነቱ መለያ የሆነ ጉንደር/አምባር እጁ ላይ ይደረግለታል/ያደርጋል። ንጉሥ በመሆኑም «ኽጉንደር ንጉሥ» በሚል ስያሜ ሲጠራ/ሲታወቅ ኖሮአል። ዛሬ ሐረጉ «አዝማች» በሚል ቃል ተተክቶ ባህላዊ መሪዎቹ በዚህ የማዕረግ ስም ይጠራሉ/ይታወቃሉ። ዛሬም ቢሆን ኃላፊዎቹ ባህላዊ አመራር፣ አስተዳደር፣ ዳኝነት፣ ሽምግላና አስታራቂነት ወዘተ. አገልግሎት ይሰጣሉ። በገጠሩ መሪዎቹ ሙሉ ጊዜያቸውን ለሕዝብ አገልግሎት ሲያውሉ ሕዝቡ የሙያ፣ የጉልበትና ወዘተ. አገልግሎት ያበረክትላቸዋል።

## 2.5 ኽተራት፣

የጦርነት፣ ያለመግባባት፣ የግጭት፣ የጭቅጭቅ ወዘተ. በጊዜያዊነት ማስታገሻ/መግቻ/ ማቆሚያ ባህላዊ ሥርዓት ነው። ሁኔታውም ስምምነት ለመፍጠር፣ ምህረት ለማውረድ ጊዜ ይሰጣል።





## 2.6 ውኪር፣

«የምሽት ሸንጎ»፣ በየምሽቱ/በየማታው ያቅራቢያ ጎረቤቶች በአካባቢው አዛውንት/ሽማግሌ ቤት በመሰባሰብ ስለሥራ፣ አካባቢ፣ አገር፣ ደኅንነት፣ ታሪክ፣ ባህል ወዘተ. የሚወያዩበት/የሚመካከሩበት መድረክ

▹ → **ማስታወሻ**

መፍቻ፣ ትርጉም፣ ማብራሪያና መግለጫ የሚሹ ቃላትና ሐረጐች በርካታ በመሆናቸው የእነዚህና የሌሎችም ቃላትና ሐረጐች መፍቻና ማብራሪያ በዕዝልነት ተያይዘዋል። (ዕዝል ሰባትን ይመለከተዋል።)

ምዕራፍ ሁለት

## ጋብቻና ተዛማጅ ጉዳዮች

### አንቀጽ ሦስት

### 3. ጋ ብ ቻ

3.0 የጉራጌ ባህል የጋብቻ ሥነ-ሥርዓት እንዲከበር እንደጊዜው ሁኔታ እያስተካከለ የሚፈጽምበት ሜራ አለው።

### 3.1 ቺግ/ፍጥምጥም

ቺግ/ፍጥምጥም በሚደረግበት ወቅት (በመተጫጨት ጊዜ) የተጋቢዎች ሙሉ ፈቃደኝነት ያለበት መሆን ይገባዋል/አለበት።

ሀ. በቺግ /በቃል ማሠሪያ ጊዜ ድግስና ከፍተኛ ወጪ አይኑር።

ለ. አንዲት ልጃገረድ የታጨች መሆንዋን የሚገልጽ ምልክት መኖር አለበት። ይህም ምልክት ቺግ /ቃል ማሠሪያ እንደተፈጸመ እጮኛዋ ከፍተኛ ወጪን የማያስከትል አንድ ሙሉ ልብስ ይስጣት/ያልብሳት።

### 3.2 የተጫጭቶ መቆያ ገደብ

አንዲት የታጨች ልጃገረድ ከታጨችበት ጊዜ ጀምሮ በአንድ ዓመት ውስጥ አግቢው ጋብቻቸው እንዲፈጸም ማድረግ አለበት። በቺግ አጭቶ አላገባም ቺጉን አፍርሼአለሁ ካለ ግን የሞራል ካሣ ያንቀሮፉት ተብሎ ብር 1000 / አንድ ሺህ ብር/ እና ሌሎች ወጪዎችም ቢኖሩ ከፍሎ ውላቸው ይፈርሳል። አንድ ዓመት ከጠበቀች በኋላም አንቂት አይኑርባት። ይህ ድንጋጌ በሁለቱ ተጋቢዎችና በቤተሰቦቻቸው ስምምነት





የሚደረገው የጊዜ መራዘምን አይመለከትም። በዚህ የተደነገገ ሜራ በሴትዋም ላይ የፀና ነው።

### 3.3 ኧገንየ

ኧገንየ ያስከተለው ችግር ስላልቀረበ እንደነበር ይቀጥል።

### 3.4 አግኖት/ሠርግ

ሀ. ሠርግ ከጉራጌ ባህልና የኤኮኖሚ አቅም ውጪ የሆኑ በአዲስ መልክ በአገር ቤት የተከሰቱትን /የመሐረብ፣ የበግ፣ የአበባ፣ የዳቦ ወዘተ... የተባሉ ከፍተኛ ወጪን የሚጠይቁ አዲስ-መጥ ሥርዓቶች ተወግደዋል።

ለ. አንዲት ልጃገረድ ስትዳር ወላጆችዋ ይዛቸው የምትሄድ ቁሳቁሶችን አደራጅተውና አሟልተው እንዲሰጡ ግዴታ የለባቸውም። ስለዚህ ወላጆች ልጃቸውን አጥበው ይስጡ።

ሐ. በሠርግዋ ቀን አግቢው ሙሽሪትን አንድ ሙሉ ልብስ ማልበስ አለበት።

መ. በሠርጉ ዕለት መገኘት ያለባቸው አዠመኝና መሣይት /የወንድና የሴት ሚዜዎችና አጃቢዎች ብዛት ከእያንዳንዱ ክፍል ከ7-10 ሰው አይብለጥ።

### 3.5 ይፍት ኧኸርነር

ይፍት ኧኸርነር በጉራጌ ባህል ከበሬታን የሚያመለክት ስለሆነና የተፈጠረ ችግርም ስለሌለ እንደነበረ ይቀጥል፤ ከፍተኛ ወጪ የሚያስከትል ግን መሆን የለበትም።

ምዕራፍ ሁለት

## ጋብቻና ተዛማጅ ጉዳዮች

### አንቀጽ ሦስት

### 3. ጋ ብ ቻ

3.0 የጉራጌ ባህል የጋብቻ ሥነ-ሥርዓት እንዲከበር እንደጊዜው ሁኔታ እያስተካከለ የሚፈጽምበት ሤራ አለው፡፡

### 3.1 ቺግ/ፍጥምጥም

ቺግ/ፍጥምጥም በሚደረግበት ወቅት (በመተጫጨት ጊዜ) የተጋቢዎች ሙሉ ፈቃደኝነት ያለበት መሆን ይገባዋል/አለበት፡፡

ሀ. በቺግ /በቃል ማሠሪያ ጊዜ ድግስና ከፍተኛ ወጪ አይኑር፡፡

ለ. አንዲት ልጃገረድ የታጨች መሆንዋን የሚገልጽ ምልክት መኖር አለበት፡፡ ይህም ምልክት ቺግ /ቃል ማሠሪያ እንደተፈጸመ እጮኛዋ ከፍተኛ ወጪን የማያስከትል አንድ ሙሉ ልብስ ይስጣት/ያልብሳት፡፡

### 3.2 የተጫጭቶ መቆያ ገደብ

አንዲት የታጨች ልጃገረድ ከታጨችበት ጊዜ ጀምሮ በአንድ ዓመት ውስጥ አግቢው ጋብቻቸው እንዲፈጸም ማድረግ አለበት፡፡ በቺግ አጭቶ አላገባም ቺጉን አፍርሼአለሁ ካለ ግን የሞራል ካሣ ያንቀሮፉት ተብሎ ብር 1000 / አንድ ሺህ ብር/ እና ሌሎች ወጪዎችም ቢኖሩ ከፍሎ ውላቸው ይፈርሳል፡፡ አንድ ዓመት ከጠበቀች በኋላም አንቂት አይኑርባት፡፡ ይህ ድንጋጌ በሁለቱ ተጋቢዎችና በቤተሰቦቻቸው ስምምነት





የሚደረገው የጊዜ መራዘምን አይመለከትም፡፡ በዚህ የተደነገገ ሤራ በሲትዎም ላይ የፀና ነው፡፡

### 3.3 ኧገንየ

ኧገንየ ያስከተለው ችግር ስላልቀረበ እንደነበር ይቀጥል፡፡

### 3.4 አግኖት/ሠርግ

ሀ. ሠርግ ከጉራጌ ባህልና የኤኮኖሚ አቅም ውጪ የሆኑ በአዲስ መልክ በአገር ቤት የተከሰቱትን /የመሐረብ፣ የበግ፣ የአበባ፣ የዳቦ ወዘተ... የተባሉ ከፍተኛ ወጪን የሚጠይቁ አዲስ-መጥ ሥርዓቶች ተወግደዋል፡፡

ለ. አንዲት ልጃገረድ ስትዳር ወላጆችዋ ይዛቸው የምትሄድ ቁሳቁሶችን አደራጅተውና አሟልተው እንዲሰጡ ግዴታ የለባቸውም፡፡ ስለዚህ ወላጆች ልጃቸውን አጥበው ይስጡ፡፡

ሐ. በሠርግዋ ቀን አግቢው ሙሽሪትን አንድ ሙሉ ልብስ ማልበስ አለበት፡፡

መ. በሠርጉ ዕለት መገኘት ያለባቸው አገርመኛና መሜይት /የወንድና የሴት ሚዜዎችና አጃቢዎች ብዛት ከእያንዳንዱ ክፍል ከ7-10 ሰው አይብለጥ፡፡

### 3.5 ይፍት ኧኻርነር

ይፍት ኧኻርነር በጉራጌ ባህል ከበሬታን የሚያመለክት ስለሆነና የተፈጠረ ችግርም ስለሌለ እንደነበረ ይቀጥል፤ ከፍተኛ ወጪ የሚያስከትል ግን መሆን የለበትም፡፡

3.6 ይፍት ዝፑዋረ

ሀ. በአሁኑ ጊዜ ለሠርግ ልዩ ልዩ ወጪን የሚያስከትሉ ፈሊጦች እንደተከሰቱ ሁሉ ይፍት ዝፑዋረም ከፍተኛ ወጪዎች አስከትሎ በትዳር ላይ እንቅፋት ሆኖአል:: ስለዚህ ሙሽሪት ወደ ወላጆችዋ ቤት ለይፍት ዝፑዋረ ሄዳ ወደ ተዳረችበት ቤትዋ ስትመለስ ለባልዋ ወላጆችና ቤተሰብ ምንም ዓይነት ቁሳቁስ ወይም ገንዘብ ይዛ እንድትመለስ ግዴታ የለባትም:: ስለሆነም ምንም ገንዘብ ወይም ቁሳቁስ ይዛ አትምጣ:: ይዞ መምጣትም በሜራ የተከለከለ ነው::

ለ. ሙሽሪት ሦስት ወር በጫጉላ ከቆየች በኋላ ለይፍት ዝፐዋረ ወደ ወላጆችዋ ትሂድ:: ለባልዋ ወላጆችና ለሌሎችም ምንም ይዛው የምትመለስ ቁሳቁስ ወይም ገንዘብ የማምጣት ግዴታዋ በሜራ የተነሣላት ስለሆነ ለይፍት ዝፐዋረ ከሄደችበት ቀን ጀምሮ ሙሽሪት በአንድ ወር ውስጥ ወደ ቤትዋ መመለስ አለባት::

3.7 ቢተር (ትዳር ይዞ ጉጆ መውጣት)

ከወላጆቻቸው ጋር ይኖሩ የነበሩ ወንድና ሴት በጉራጌ የጋብቻ ሜራና እያንዳንዳቸው በሚከተሉት እምነት መሠረት ተጋብተው ጎጆ ሲወጡ ወላጆች/ቤተሰቦች ለልጆቻቸው ቢተር መውጫ መስጠት አልተከለከለም:: በተለይም የወንዱ ወላጆች/ቤተሰቦች አቅማቸው በፈቀደ መጠን ልጆቻቸው ቢተር እንዲወጡና እንዲቋቋሙ የማድረግ ኃላፊነት፣ግዴታ አለባቸው::





## አንቀጽ አራት

4. የተከለከለ የጥብ/የቤተ-ዘመድ ጋብቻ

4.0 የጥብ ሐረግ /የቤተ-ዘመድ ጋብቻ ክልክል ወሰን ስላለው ቺጫው መከበር አለበት::

4.1 በጉራጌ ባህልና ሥርዓት የአንድ ጥብ ቀጥተኛ ተወላጆች አይጋቡም::

4.2 በአባታቸው ወገን በአንድ ጥብ ውስጥ የአንድ ቤት ተወላጆች የሆኑ ወንድና ሴት የትውልድ ዘርፋቸው ምንም ያህል ቢራራቅ መጋባት አይችሉም::

4.3 በዚህ ቺጫ ውስጥ የተከለከለውን ጥሰው ቢጋቡ የጋብቻው አፈጻጸም የተወገዘ ስለሆነ ጥቫቸው እንዲፋቱ ማድረግ አለበት::

4.4 የጉራጌን ቺጫ ጥሰው የተጋቡ ወንድና ቤት እንዲፋቱ ተጠይቀው እምቢ ካሉ ከዝምድና ውጪ ይሆናሉ:: ይህም ጥብ ተሰብስቦ ሥርዓቱን ያስፈጽማል::

4.5 አንድ ጥብ በተለያዩ ቤቶች ይከፈላል:: በሴት በኩል በአንድ ጥብ ውስጥ ከአግቢው/ከአግቢዋ ቤት የተለየ ቤት ሞነቢያ/መቸቢያ የሆነ/የሆነች በዚያው ጥብ ውስጥ ሆኖ ቤቱ የተለያየ ከሆነ መጋባት ይችላሉ::

## አንቀጽ አምስት

5. ፍቺ

5.1 የፍቺ መፈጸም ግዴታ ሲያጋጥም የባለጉዳዮቹ መብት በእኩልነት መጠበቅ አለበት::

5.2 ፍቺው ከመፈጸሙ በፊት ጉዳዩ በጉራጌ ባህል መሠረት በቤተ ዘመድ ጉባዔ መታየት አለበት::

5.3 የቤተ-ዘመድ ጉባዔ ፍቺው የማይቀር መሆኑን ካረጋገጠ ከተጋቡ ጊዜ ጀምሮ በጋራ ያፈሩትን ንብረት እኩል ይካፈላሉ::

5.4 ለጋብቻው መፍረስ ምክንያት ሆኖ የተገኘው/የተገኘችው ወገን በጋራ ካፈሩት ንብረት እኩሉን ከተካፈለ/ከተካፈለች በኋላ ለተበዳዩ/ለተበዳይዋ ወገን ከድርሻው/ከድርሻዋ ሲሦውን/ከሦስት አንዱን እጅ/በካሣ መልክ ይከፍላል/ትከፍላለች::

5.5 ለረዥም ዘመን ተጋብተውና ቤተሰብና ንብረት አፍርተው ከኖሩ ባልና ሚስት መካከል ባልየው ሚስቱን ቤት ለቀሽ ውጪልኝ ቢላት መውጣት የለባትም:: ባልየው ከፈለገ ቤቱን ለሴትየዋ ለቅቆ ወጥቶ በሌላ ቦታ መኖሪያ መመሥረት ይችላል::

5.6 <u>ባለትዳር ያማገጠ/ያማገጠች</u>

ባለትዳር ሴት ያማገጠ/የደፈረ ወይም ባለትዳር ወንድ ያማገጠች ሴት ከብር 3,000-5,000 (ከሦስት ሺህ እስከ አምስት ሺህ ብር) ካሣ ይከፍላል/ትከፍላለች::

5.7 <u>አ ን ቂ ት</u>

5.7.1 በትዳር ላይ ያለች የሌላ ሰው ሚስት ነጥቆ የወሰደ ሰው ትዳሩ ለፈረሰበት ባል ብር 10,000 (አሥር ሺህ ብር) መክፈል አለበት:: በዚሁ አንቂቱ ያበቃል::

5.7.2 አንድ ወንድ ሚስቱን ማስተዳደር ካልቻለና እንዲፈታት ጠይቃው እምቢ ካለ ወይም ፍቺው ካልፈጸመላት ሁለት ዓመት ከጠበቀች በኋላ አንቂት አይኖርባትም::

5.8 <u>ወ ግ የ ት /ድረፊት</u>

አንዲት ሴት በወግየትነት ሲያገባት ከሚጠይቃት ወንድ





ጋር በቀጥታ ትነጋገራለች፤ አስፈላጊ ሲሆንም በውሉ የሚረዳትን ዘመድ ይዛ መቅረብ ትችላለች:: ስለዚህ ሁለቱ ተጋቢዎች ተስማምተው ጋብቻቸውን ይፈጽሙ::

## አንቀጽ ስድስት

6. <u>ዝማጅ /የልጃገረድ ጠለፋ</u>

6.1 <u>ለአቅመ-ሔዋን የደረሰች ግን ያልታጨች ልጃገረድን የጠለፈ፣</u>

ሀ. ካገ ደፈራት ብር 5,000 (አምስት ሺህ ብር) ካሣ ይከፍላል::

ለ. ከደፈራት ብር 10,000 (አሥር ሺህ ብር) ካሣ ይከፍላል::

6.2 <u>የታጨች ልጃገረድን የጠለፈ</u>

ሀ. ከደፈራት ለልጅትዋ ብር 10,000 /አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

ለ. ለወንድ ሕጋዊ እጮኛዋ ብር 10,000 /አሥር ሺህ ብር/ካሣ ይከፍላል::

6.3 <u>ለአቅመ-ሔዋን ያልደረሰች ሴት ልጅን የጠለፈ</u>

ሀ. ጠላፊው ካልደፈራት ብር 10,000 /አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

ለ. ከደፈራት የሕክምናን ወጪ ችሎ በተጨማሪ ብር 15,000 /አሥራ አምስት ሺህ ብር/ ለተደፈረችው ሴት ልጅ ካሣ ይከፍላል::

## አንቀጽ ሰባት

7. <u>የጋብቻ ሜራው በሃይማኖት ከሚፈፀሙ ጋብቻዎች ጋ[ር] ያለው ዝምድና</u>

በእስልምናም ሆነ በክርስትና ሃይማኖት መሠረት የሚፈጸመ[ው] የጋብቻ ሥርዓቶች በዚያው በኩል የሚፈጸሙ እን[ደ]... ያስተጋቢዎቹ ፈቃድ በጉራጌ ቄጫ ውስጥ አይገቡም[፡] ስለሚጋቡ ወንድና ሴት የዝምድና ሐረግ ግን ያው በጉራ[ጌ] ቄጫ መሠረት ብቻ ይሆናል::

## አንቀጽ ስምንት

8. <u>የጋብቻና ተዛማጅ ሜራዎች ተፈጻሚነት ወሰን</u>

በቄጫው የተካተቱ የጋብቻና የተዛማጅ ጉዳዮች ሜራ በጉራ[ጌ] ተወላጆች ሁሉ መከበር አለባቸው::



# ምዕራፍ ሦስት

## <u>ሐዘንና ተዝካር</u>

## አንቀጽ ዘጠኝ

9. <u>ቢኼ/ልቅሶ</u>

9.0 ለቅሶ በጉራጌ ባህል የልጅ፣ የአዋቂ፣ የሴት፣ የወንድ፣ በዕድሜ፣ በማዕረግ፣ በታሪክ ደረጃ ወዘተ... መሠረት ልዩ ልዩ የለቅሶ ሥርዓት እንዳለ ይታወቃል:: ዳሩ ግን በአሁኑ ጊዜ ሥርዓቱ አልተጠበቀም::

9.1 <u>ኧቁም ቢኼ</u> እንደሚቹ የማኅበራዊ አገልግሎትና ታዋቂነት ሁኔታ የሚፈጸም ስለሆነ የነበረው ሥርዓት ተጠብቆ ይቀጥል::

9.2 በለቅሶ ወቅት የተዳሩ ሴቶች ልጆች ለሐዘን መስተንግዶ የሚሆን የሚታረድ ከብትና እህል ይዘው እንደሚመጡና ያመጡትም ንብረት ለቅሶ ሲገቡ አብሮ እንዲታይ ስለሚደረግና ይዘው የመጡትም ለተከታዮቻቸው መስተንግዶ ስለሚውል ሐብት በሌላቸው እህቶች ላይ ተጽዕኖ ከማሳደሩም በላይ በለቅሶ ጊዜ ያጣላቸዋል ተብሎአል:: በመሠረቱ ያለው ሰው ለመስተንግዶ የሚሆን ነገር ይዞ ቢመጣ የቤተሰብ መረዳዳትን ያመለክታል። ዳሩ ግን ይህ ሥርዓት ለጉራና የሌለውን ሰው ዝቅ አድርጎ ለማሳየት መሆን የለበትም:: መስተንግዶውም ለሁሉም እኩል መሆን አለበት:: ሐብት የሌላቸው ለመግደርደር ዕዳ ቢገቡ እርግማን ስለሚደርስባቸው መጠንቀቅ አለባቸው::

9.3 በአንዳንድ ቦታ በለቅሶ ጊዜ ክመጠን በላይ የሆነ ልዩ ድግሥ ይደረጋል:: ይህ ድርጊት የሟቹን ቤተሰብ የሚጐዳ ከፍተኛ ሐሜታም ያስከተለና «በገንዘብ ጡር ማውጣት» ስለሆነ ሰዎች የዚህ ዓይነቱን ድግሥ ከማዘጋጀት ይቆጠቡ::

## አንቀጽ ሰባት

7. <u>የጋብቻ ሤራው በሃይማኖት ከሚፈፀሙ ጋብቻዎች ጋ( ያለው ዝምድና</u>

በእስልምናም ሆነ በክርስትና ሃይማኖት መሠረት የሚፈጸመ የጋብቻ ሥርዓቶች በዚያው በኩል የሚፈጸሙ እን ያስተጋቢዎቹ ፈቃድ በጉራጌ ቹጫ ውስጥ አይገቡም፣ ስለሚጋቡ ወንድና ሴት የዝምድና ሐረግ ግን ያው በጉራ ቹጫ መሠረት ብቻ ይሆናል።

## አንቀጽ ስምንት

8. <u>የጋብቻና ተዛማጅ ሤራዎች ተፈጻሚነት ወሰን</u>

በቹጫው የተካተቱ የጋብቻና የተዛማጅ ጉዳዮች ሤራ በጉራ ተወላጆች ሁሉ መከበር አለባቸው።



## ምዕራፍ ሦስት

<u>ሐዘንና ተዝካር</u>

## አንቀጽ ዘጠኝ

9. <u>ቢኼ/ልቅሶ</u>

9.0 ለቅሶ በጉራጌ ባህል የልጅ፣ የአዋቂ፣ የሴት፣ የወንድ፣ በዕድሜ፣ በማዕረግ፣ በታሪክ ደረጃ ወዘተ... መሠረት ልዩ ልዩ የለቅሶ ሥርዓት እንዳለ ይታወቃል። ዳሩ ግን በአሁኑ ጊዜ ሥርዓቱ አልተጠበቀም።

9.1 <u>እቁም ቢኼ</u> እንደሚቹ የማኅበራዊ አገልግሎትና ታዋቂነት ሁኔታ የሚፈጸም ስለሆነ የነበረው ሥርዓት ተጠብቆ ይቀጥል።

9.2 በለቅሶ ወቅት የተዳሩ ሴቶች ልጆች ለሐዘን መስተንግዶ የሚሆን የሚታረድ ከብትና እህል ይዘው እንደሚመጡና ያመጡትም ንብረት ለቅሶ ሲገቡ አብሮ እንዲታይ ስለሚደረግና ይዘው የመጡትም ለተከታዮቻቸው መስተንግዶ ስለሚውል ሐብት በሌላቸው እህቶች ላይ ተጽዕኖ ከማሳደሩም በላይ በለቅሶ ጊዜ ያጣላቸዋል ተብሎአል። በመሠረቱ ያለው ሰው ለመስተንግዶ የሚሆን ነገር ይዞ ቢመጣ የቤተሰብ መረዳዳትን ያመለክታል። ዳሩ ግን ይህ ሥርዓት ለጉራና የሌለውን ሰው ዝቅ አድርጎ ለማሳየት መሆን የለበትም። መስተንግዶውም ለሁሉም እኩል መሆን አለበት። ሐብት የሌላቸው ለመግደርደር ዕዳ ቢገቡ እርግማን ስለሚደርስባቸው መጠንቀቅ አለባቸው።

9.3 በአንዳንድ ቦታ በለቅሶ ጊዜ ክመጠን በላይ የሆነ ልዩ ድግሥ ይደረጋል። ይህ ድርጊት የሟቹን ቤተሰብ የሚጐዳ ከፍተኛ ሐሜታም ያስከተለና «በገንዘብ ጡር ማውጣት» ስለሆነ ሰዎች የዚህ ዓይነቱን ድግሥ ከማዘጋጀት ይቆጠቡ።

9.4 ለለቅሶ ከሐገር ቤት ወደ ከተማ ከከተማም ወደ ሐገር ቤት ሰው በብዛት ይመጣል፤ ይሄዳልም:: በአሁኑ ጊዜ ይህ ሁኔታ በጣም በዝቶአል:: በማኅበራዊና በኢኮኖሚም ረገድ ከፍተኛ ችግር አስከትሎአል:: ለልቅሶ ከሁለቱም አቅጣጫ የሚጓዘው ሰው በቤተሰብ አካባቢ እንዲወሰን ጉራጌ ጥረት እንዲያደርግ ጥብቅ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል::

9.5 በለቅሶ ጊዜ በጉራጌ ባህል ስልስት የለም፤ በአሁን ጊዜ አልፎ አልፎ ሲስተገበር ስለሚስተዋል፤ ስልስት ተከልክሎአል፤ ቀርቶአል::

9.6 የሞተ ሰው መቅበሪያ ቀን ከመጠን በላይ መራዘም የለበትም:: ሆኖም ቤተ-ዘመድ ማሳወቂያውና ልዩ ልዩ ሁኔታዎችን ተከትሎ ይወሰን:: የለቅሶ ማንሻው ጊዜ 5 ቀን ሆኖ ለአዝማች/ለጉንደር ንጉሥ ግን 7 ቀን ይሁን::

## አንቀጽ አሥር

## 10. ተዝካር

10.1 በሃይማኖቶች በኩል ያሉ ሁኔታዎች እንደተጠበቁ ሆነው ለተዝካር የሚደረገው ከፍተኛ ወጪ አስፈላጊ አይደለም:: ሟችን ለማስታወስ ያህል ብቻ ከሃይማኖት ጋር የተያያዙት ቢፈጸሙ ይበቃል:: ስለዚህ ለተዝካር መደገስ ክልክል ነው፤ ተዝካር ቀርቶአል::

10.2 ስለ ተዝካር ከዚህ በላይ የተወሰነውን ሤራ ጥሶ ተዝካር ያወጣ የጉራጌ ተወላጅ ውግዘቱ እንደተጠበቀ ሆኖ ብር 2,000 /ሁለት ሺህ ብር/ መቀጫ ይከፍላል::

10.3 ሐዘንና ተዝካር በጉራጌ ሕዝብ ላይ ችግሮችን በማስከተላቸው በዚህ ምዕራፍ የተመለከቱት ሤራዎች ተደንግገዋል፤ በመሆኑም በሁሉም የጉራጌ ተወላጅ ተፈጻሚነት ማግኘት አለባቸው::





## አንቀጽ አሥራ አንድ

## 11. በደስታና በሀዘን ወቅት ስለሚተኮሱ መሣሪያዎች

በደስታ፣ በሠርግ፣ በለቅሶና በቤተክርስቲያን በዓል አከባበር ወቅት ጠብመንጃ ወይም ሽጉጥ መተኮስ የተወገዘ ነው:: ምክንያቱም በሰው ሕይወትና በንብረት ላይ አደጋ ያደርሳል:: ስለዚህ ይህንን ውሳኔ የጣሰ ብር 500 /አምስት መቶ ብር/ ይቀጣል:: ባደረሰውም የሰው ወይም የንብረት አደጋ በየደረጃው ይጠየቃል::



## ምዕራፍ አራት

## ኢኮኖሚና ማህበራዊ ጉዳዮች

የኢኮኖሚና የማህበራዊ ጉዳዮች የሕዝቡን ሕይወት በቀጥታ የሚነኩ በመሆናቸው በቂጫ ውስጥ ገብተዋል:: ዝርዝራቸው ጥቂት ባይሆንም ለምሳሌ ያህል ከፊሎቹ ተካተዋል::

### አንቀጽ አሥራ ሁለት

### 12. ኤኮኖሚ ልማት

#### 12.1 በተለይ ባህርዛፍ፣ ኧሰትና ጫት ተከላን በተመለከተ

12.1.1 የጉራጌ ብሔረሰብ ዋና የምግብ ተክሉ ኧሰት ቢሆንም ሌሎች ሰብሎች በሁለተኛ ደረጃ አምርቶ ይጠቀማል::

12.1.2 በአሁኑ ጊዜ ለኧሰትና ለአዝርዕት የሚሰጠው እንክብካቤ ደረጃ ዝቅ ብሎ ወደ ጫትና ባሕርዛፍ ተክሎች በማዘንበሉ በአካባቢው የምግብ እጥረት ችግር በጉልህ እየታየ በመሆኑ አፋጣኝ የእርምት እርምጃ መወሰድ አለበት:: ዛሬ ጫትና ባሕርዛፍ ጥሬ ገንዘብ ቢያመጡም የሚያስከትሉትን ጉዳት ማስተዋል ይገባል::

12.1.3 ባሕርዛፍ ብዙ ውሃ ስለሚያስፈልገውና ሥሩም ረጅም ቦታ ድረስ ሄዶ ውሃ ስለሚስብ በኧሰትና በሌሎች ሰብሎች አጠገብ መተከሉ የምግብ ሰብሎችን ስለሚጎዳ ከሰብሎች ራቅ ባለቦታ ብቻ ይተከል::

12.1.4 የምንጭ ውሃ ባለበት አጠገብና በሁለት ባለቦታዎች ወሰን ላይ ባሕርዛፍ አይተከል::

12.1.5 የጫት ተክልም የኧሰትና የጉመን ሥፍራዎችን ወስዶ የምግብ እጥረት ደረጃ የተባባሰ እንዳይሆን





አተካከላቸው የምግብ ሰብሎችን በሚጎዳ ወይም ደረጃውን ዝቅ በሚያደርግ አኳኋን አይሁን::

12.1.6 የምግብ ሰብሎች ምርት እንዲበዛ አምራች የሆነ ሁሉ በቂ ትኩረት ሰጥቶ እንክብካቤ ያድርግ::

12.1.7 የደን ልማት መኖር አስፈላጊ ስለሆነ ለቦታው ተስማሚ የሆኑ ዝርያዎች በሥርዓት መተከል አለባቸው፤ ለአገር-በቀል ዝርያዎች ትኩረት በመስጠት እንዲራቡ ይደረግ::

12.1.8 የጉራጌ ባህላዊ ምግቦች በአገር ውስጥና በውጭ አገር በከፍተኛ ደረጃ ታዋቂነታቸውና ተፈላጊነታቸው በተረጋገጠበት በአሁኑ ወቅት በተለይ ተፈላጊ የሆኑት የውሳና የአጥሜጥ ምርት ከምንጩ በጣም ተዳክሞ ስለሚታይና አሳሳቢም ስለሆነ በቂጫ ውስጥ ሥፍራ እንዲኖረው ተወስኖአል::

12.1.9 የኧሰት ውጤቶች ተፈላጊነት እያደገ ሲመጣ ምርቱ እያሽቆለቆለ መሄዱ በመጀመሪያ ደረጃ በቂ ምግብ ባለማግኘቱ የገጠር ተወላጁ ጉዳት ላይ ወድቆአል:: ቀጥሎም ኧሰት በብዛትና በጥራት ቢያመርት ኖሮ ከቤተሰቡ ፍጆታ ተርፎት ወደ ገበያ በማውጣት ያገኘው የነበረ ገቢ ቀርቶበታል:: ስለዚህ ኧሰት የተፈጥሮ ችግሮችንም መቋቋም የሚችል በመሆኑ በተፈላጊነቱ መጠን በብዛትና በጥራት እንዲመረት ጉዳዩ የሚመለከታቸው ምርቱ እንዲያድግ ያልተቆጠበ ድጋፍ እንዲያደርጉና ገበሬውም እውነታውን ተረድቶ የኧሰት ምርቱን እንዲያጉለብት በዚህ ቂጫ በተደጋጋሚ ብርቱ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል::

12.1.10 የኧሰትን ዕድገት የሚያፋጥኑና የሚያጠቁትን በሽታዎች መከላከል ብሎም ማጥፋት የሚችሉ ጥናቶች እንዲደረጉ በምሁራን ላይ ከባድ አደራ

የተጣለ ሲሆን፣ ውጤቶቹንም ሁሉም ተባብሮ እንዲተገብራቸው ተወስኖአል።

## 12.2. ማህበራዊና ኤኮኖሚያዊ የልማት ሥራዎች እንዲስፋፉ መርዳት

በጉራጌ አካባቢ የመንገዶች፡ የትምህርት ቤቶችና የአንዳንድ ሌሎች የልማት ሥራዎች የተካሄዱና በመካሄድ ላይ ቢኖሩም በተለይ የአካባቢውን ሶሺዮ-ኢኮኖሚ ዕድገት የሚያፋጥኑ የአምራች ድርጅቶች መመሥረት ወሳኝ ወቅት ነው። ስለዚህ በአካባቢው ልዩ ልዩ ሙያ የተማሩና በመማር ላይ ላሉ ወጣት ወንዶችና ሴቶች ልጆች ሥራ የሚፈጥር አነስተኛ፣ መካከለኛና ከፍተኛ አግሮ-ኢንዱስትሪዎችን በማቋቋም ረገድ ተወላጆች ዕውቀታቸውንና ገንዘባቸውን አስተባብረው ራሳቸውን ጠቅመው ወገናቸውንም ሥራ በመፍጠር እንዲረዱ ብርቱ ማሳሰቢያ ተሰጥቶ አደራም ተጥሎአል።

## 12.3. በትብብር አካባቢን የማልማት ባህልን ማጉልበት

ጉራጌ በባህሉ እንደጀዝ/ወንፈል በመሰለ አሠራር በመረዳዳት ሲሠራ እንደነበረ ቢታወቅም የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅትና ሌሎችም ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ ሕዝባዊ የልማት አውታሮች በበለጠ ተስፋፍተው በጉሕራልድ የታቀዱትም ፕሮግራሞች ተግባራዊ ሆነው የህብረተሰቡን የኑሮ ደረጃ ለማሻሻል በተጠናከረ ሁኔታ እንዲያግዙ በሚደረገው ጥረት የሁሉም ሰው አስተዋጽኦ ይጠይቃል። የጉራጌ ሕዝብ ራስአገዝ ልማት ድርጅት በአዲሱ ዓላማዎች፣ ፕሮግራሞች፣ ዕቅዶችና ደንቦች መሠረት ዳብሮ ሁለገብ የልማት ሥራዎችን እንዲያራምድ መዋቅሩም ታች ድረስ ደርሶ እንዲተገበር ተወስኖአል። የትራንስፖርት ዘርፍም የገቢ ምንጩ ተጠናክሮና ሌሎችም የገቢ ምንጮች ተፈጠረው ጉሕራልድ በተጉላበት መልኩ ወደፊት ይቀጥል።





# አንቀጽ አሥራ ሦስት

## 13. ማህበራዊ ኃላፊነቶች

ማህበራዊ ኃላፊነቶች ዝርዝራቸው በዛ ያለ ነው። ለምሳሌ የሕፃናት አስተዳደግና እንክብካቤ፣ ወላጆችን መርዳትና መጦር፣ አካለስንኩላንን መርዳት የመሳሰሉ ልምዶች ሊጠናከሩ ይገባል።

### 13.1 ልጆችን የማስተማር ግዴታ

13.1.1 ጉራጌ በባህሉ መሠረተ ተረዳድቶ ትምህርት ቤቶችን በብዛት ሠርቶ በጉደለም የድጉማ መምህራን ቀጥሮ ልጆቹን ማስተማር ቀደም ሲል የጀመረ ቢሆንም ጾታ ሳይለይ አቅም በፈቀደ መጠን ወላጆች ልጆቻቸውን የማስተማርና የማሳደግ ግዴታ እንዳለባቸው በጉራጌ ቺጫ ተደንግጉአል።

13.1.2 ሕዝቡ ባሠራቸው ትምህርት ቤቶች መማር ያለባቸው ልጆች ሁሉ የዚያን ደረጃ ትምህርት ሳይጀምሩ ወይም ሳያጠናቅቁ በጨቅላ ዕድሜያቸው ለሥራ ወደ ከተማ የሚኅርፉት ሕፃናት ብዛት በአሁኑ ጊዜ ከፍተኛ ስለሆነ ይህ ፍልሰት የልጆቹን የወደፊት ዕድልና ዕድገት ሁኔታን የሚያዛባ ስለሆነ ወላጆችና ህብረተሰቡ የመግታት ግዴታ አለባቸው።

13.1.3 የጉራጌ ሕፃናት ከአካባቢያቸው መፍለስ የሚያስከትለው ሶሺዮ-ኢኮኖሚ ጉዳዮችና መፍትሔያቸው በዝርዝር መጠናቱ እንደተጠበቀ ሆኖ፣

ሀ. አሁን ጊዜው ቀድሞ ከነበረበት የተለወጠ ስለሆነ ከሊስትሮነት ተነስቶ ከፍተኛ ደረጃ መድረስ የማይቻለበት ወቅት በመደረሱ፣

የተጣለ ሲሆን፣ ውጤቶቹንም ሁሉም ተባብሮ እንዲተገብራቸው ተወስኖአል።

## 12.2. ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ የልማት ሥራዎች እንዲስፋፉ መርዳት

በጉራጌ አካባቢ የመንገዶች፡ የትምህርት ቤቶችና የአንዳንድ ሌሎች የልማት ሥራዎች የተካሄዱና በመካሄድ ላይ ቢኖሩም በተለይ የአካባቢውን ሶሺዮ-ኢኮኖሚ ዕድገት የሚያፋጥኑ የአምራች ድርድቶች መመሥረት ወሳኝ ወቅት ነው። ስለዚህ በአካባቢው ልዩ ልዩ ሙያ የተማሩና በመማር ላይ ላሉ ወጣት ወንዶችና ሴቶች ልጆች ሥራ የሚፈጥር አነስተኛ፣ መካከለኛና ከፍተኛ አግሮ-ኢንዱስትሪዎችን በማቋቋም ረገድ ተወላጆች ዕውቀታቸውንና ገንዘባቸውን አስተባብረው ራሳቸውን ጠቅመው ወገናቸውንም ሥራ በመፍጠር እንዲረዱ ብርቱ ማሳሰቢያ ተሰጥቶ አደራም ተጥሎአል።

## 12.3. በትብብር አካባቢን የማልማት ባህልን ማጉልበት

ጉራጌ በባህሉ እንደጌዝ/ወንፈል በመሰለ አሠራር በመረዳዳት ሲሠራ እንደነበረ ቢታወቅም የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅትና ሌሎችም ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ ሕዝባዊ የልማት አውታሮች በበለጠ ተስፋፍተው በጉሕራልድ የታቀዱትም ፕሮግራሞች ተግባራዊ ሆነው የህብረተሰቡን የኑሮ ደረጃ ለማሻሻል በተጠናከረ ሁኔታ እንዲያግዙ በሚደረገው ጥረት የሁሉም ሰው አስተዋጽኦ ይጠይቃል። የጉራጌ ሕዝብ ራስአገዝ ልማት ድርጅት በአዲሱ ዓላማዎች፣ ፕሮግራሞች፣ ዕቅዶችና ደንቦች መሠረት ዳብሮ ሁለገብ የልማት ሥራዎችን እንዲያራምድ መዋቅሩም ታች ድረስ ደርሶ እንዲተገበር ተወስኖአል። የትራንስፖርት ዘርፍም የገቢ ምንጩ ተጠናክሮና ሌሎችም የገቢ ምንጮች ተፈጥረው ጉሕራልድ በተጉላበት መልኩ ወደፊት ይቀጥል።





# አንቀጽ አሥራ ሦስት

## 13. ማህበራዊ ኃላፊነቶች

ማህበራዊ ኃላፊነቶች ዝርዝራቸው በዛ ያለ ነው። ለምሳሌ የሕፃናት አስተዳደግና እንክብካቤ፣ ወላጆችን መርዳትና መጦር፣ አካለስንኩላንን መርዳት የመሳሰሉ ልምዶች ሊጠናከሩ ይገባል።

### 13.1 ልጆችን የማስተማር ግዴታ

13.1.1 ጉራጌ በባህሉ መሠረት ተረዳድቶ ትምህርት ቤቶችን በብዛት ሠርቶ በጉደለም የድጉማ መምህራን ቀጥሮ ልጆቹን ማስተማር ቀደም ሲል የጀመረ ቢሆንም ጾታ ሳይለይ አቅም በፈቀደ መጠን ወላጆች ልጆቻቸውን የማስተማርና የማሳደግ ግዴታ እንዳለባቸው በጉራጌ ቼጫ ተደንግጉአል።

13.1.2 ሕዝቡ ባሠራቸው ትምህርት ቤቶች መማር ያለባቸው ልጆች ሁሉ የዚያን ደረጃ ትምህርት ሳይጀምሩ ወይም ሳያጠናቅቁ በጨቅላ ዕድሜያቸው ለሥራ ወደ ከተማ የሚኅርፉት ሕፃናት ብዛት በአሁኑ ጊዜ ከፍተኛ ስለሆነ ይህ ፍልሰት የልጆቹን የወደፊት ዕድልና ዕድገት ሁኔታን የሚያዛባ ስለሆነ ወላጆችና ህብረተሰቡ የመግታት ግዴታ አለባቸው።

13.1.3 የጉራጌ ሕፃናት ከአካባቢያቸው መፍለስ የሚያስከትለው ሶሺዮ-ኢኮኖሚ ጉዳዮችና መፍትሔያቸው በዝርዝር መጠናቱ እንደተጠበቀ ሆኖ፣

ሀ. አሁን ጊዜው ቀድሞ ከነበረበት የተለወጠ ስለሆነ ከሊስትሮነት ተነስቶ ከፍተኛ ደረጃ መድረስ የማይቻለበት ወቅት በመደረሱ፣

ለ. ተማሪ ትምህርት ይማር የነበረው ለሥራ /ለደመወዝ ሲል ስለነበረና አሁን ግን ይህ ዕድል የቀረና ሥራ ማግኘት በውድድር ላይ በመመሥረቱ፣

ሐ. መማር ሙያን በማዳበር የተለያዩ ሥራዎችና ንግድን በተሻለ ሁኔታ ለማካሄድ ወሳኝነት ያለው በመሆኑ፣

መ. ወደሌላ ቦታም ሄዶ ተወዳድሮ ሥራ ለማግኘት እንደ ሁኔታው በየደረጃው ያሉ ትምህርት ፕሮግራሞችን ማጠናቀቅ ስለሚጠይቅ፣

ሠ. ህብረተሰቡ ህብቱና ጉልበቱን አፍስሶ ያሠራቸው ትምህርት ቤቶች የልጆቹ መማሪያ መሆን ስላለባቸው ወላጆች፣ ህብረተሰቡና ልጆች ተባብረውና ተግባብተው ትምህርት በየደረጃው እንዲጠናከር እንዲያደርጉ ተወስኖአል::

## 13.2 ወላጆችን የመንከባከብ ኃላፊነት

ልጆች እናትና አባታቸውን ባላቸው አቅም የመንከባከብ ኃላፊነት አለባቸው:: አባትና እናታቸውን ባለአቅማቸው ያላስታወሱና ያልረዱ ልጆች በልቅሶ ጊዜ ብቻ ብቅ ብለው አለሁ አለሁ ማለት ተቀባይነት ስለሌለው ተገቢውን ድጋፍ እንዲያደርጉ ተወስኖአል::

## 13.3 የባህል ቅርሶችን የመጠበቅ ግዴታና ኃላፊነት

13.3.1 በአሁኑ ጊዜ የጉራጌ የባህል ቅርስ የሆኑ ዕቃዎች ስለሚሸጡ በመጥፋት ላይ ናቸው:: ያሉ የባህል ዕቃዎችን ሁሉ የሚያካትት





ሙዝየም እስከሚኖር ብዙ ጊዜና ድርጅት ስለሚጠይቅ የጉራጌ ሕዝብ በየክፍሉ ብርቱ ጥረት በማድረግ የማስጠበቅና የመጠበቅ ግዴታና ኃላፊነት አለበት::

13.3.2 በየአካባቢው ውስጥ ያሉ ታሪካዊ ቦታዎችን መንከባከብና ማደራጀት፣ የተፈጥሮ መስህቦዎችን፣ ዋሻዎችንና መናፈሻዎችን ማደራጀትና መጠበቅ ያስፈልጋል:: ለዚህም የህብረተሰቡ ሚና ከፍ ያለ ነው::

13.3.3 ብዙ የጉራጌ ባሕል ቅርሶች በመጥፋት ላይ ስለሆኑ ያሉትም ሆነ የጠፉት በዓይነታቸው ተሠርተው በእንክብካቤ ይጠበቁ፣ መሠረታዊዎቹ/ኦሪጅናሎቹ በእንክብካቤ እንዲጠበቁ ሆኖ በዓይነታቸው አስመስሎ በመሥራት ቢሸጡ ገቢ ስለሚያስገኙ እንዲሠሩ ጥረት ይደረግ::

## 13.4 በበዓላት ምክንያት ስለሚታረዱ ከብቶች

13.4.1 መስቀር፣ ንኾዋርና አረፋ የመሳሰሉት በዓላት ጉራጌ በባህሉ ከፍተኛ ከበሬታ የሚሰጣቸውና ከወላጆችና ከቤተዘመድ ጋር ለመገናኘትም ትልቅ ድልድዮች ስለሆኑ በዓላቱ መከበራቸው መቀጠል አለበት::

13.4.2 በዓሎቹ በባህሉ መሠረት ይቀጥሉ ሲባልም በመስቀር፣ በንኾዋርና በአረፋ በዓላት ወቅታት አለአግባብ በብዛት የሚታረዱ ጥጃዎች፣ ጊደሮችና ወይፈኖች የአካባቢውን ኢኮኖሚ በሚመለከት አጉል ብክነትን ያስከተሉ በመሆኑ ሊታረሙ የሚገባቸው ደካማ ጉኖች መታረም አለባቸው::

13.4.3 ከዚህ በፊት በቅርብ የሚኖሩ ቤተሰቦችና ጉረቤቶች እንደ አቅማቸው ገንዘብ አዋጥተው

ከፍተኛ ስንጋ ገዝተው የበለጠ ከበሬታ ባለው አባል ቤት ወይም በወቅቱ በሚወስኑት አባል ቤት አርደው ሥጋውን ተካፍለው በዓሉን ያከብሩ ነበር:: የዚህም ጥቅሙ ተቀራርቦና ተከባብሮ መኖርን የመሰሉ በጎ ጐኖች ነበሩት:: በዛሬው ጊዜ ግን ሁኔታው ሙሉ በሙሉ ተለውጦ በአብዛኛው ቦታ ከማን አንሼ በማለት በየደጃፉ ጥጃዎችን ስለሚያርድ መሠረታዊ ባህሉ የተናጋ ከመሆኑም ባሻገር አድገው ጥጃ ሊወልዱ የሚችሉ፣ አድገው ለእርሻ ወይም ስንጋ ሊሆኑ የሚችሉትን ጥጃዎችና ወይፈኖችን በብዛት በማረድ በዓሉን ያከብራል:: ይህ ጥጃዎችን በየቤቱ የማረድ አዲስ ባህል የጉራጌን ብቻ ሳይሆን የሀገሪቱንም ኤኮኖሚ የሚጎዳ መሆኑ ግንዛቤ ስለተወሰደ የጉራጌ ተወላጅ የሆነ ሁሉ በዚህ ጉዳይ ላይ በጥብቅ አስቦበት ጥጃዎችንና ወይፈኖችን ማረዱን ትቶ እንደቀድሞው ከፍተኛ ከብቶችን በጋራ አርዶ እንዲጠቀም ተወስኖአል::

## አንቀጽ አሥራ አራት

## 14. <u>ማህበራዊ መተጋገዞች</u>

14.0 ማህበራዊ መተጋገዞች ብዛታቸው ከፍ ያለ ስለሆነ ዝርዝር ጥቅምና ጉዳታቸው ወደፊት የሚጠና ቢሆንም በተለይ <u>ወኪያን</u> በሚመለከት በቂጫው በግልጽ እንዲታይ ተደርጓል::

### 14.1 <u>ወኪያ</u>

ሀ. በጉራጌ ባህል ወኪያ ከብት ያለው ወይም በኑሮው ሻል ያለ ሰው በኑሮው ዝቅ ባለ ደረጃ የሚገኘው ሰው ኑሮውን ማቋቋም እንዲረዳው የሚያደርግ የተቀደሰ የመተጋገዣ ሥርዓት ነው:: በአሁኑ ጊዜ አንዳንድ ከብት ወኪያ የተሰጣቸው ሰዎች ከዚህ በፊት ያልነበረ ክህደት





ወይም ክርክር ስለፈጠሩ በመተጋገዣ ሥርዓቱ ላይ ችግር እንዳስከተለ ታውቆአል:: ስለዚህ ሜራ ሊወጣለት ይገባል:: <u>ቂጫውም</u> <u>ከብት ወኪያ</u> የተሰጠው ሰው ጥጃዋ ወልዳ ቢያንስ በአንድ ዙር ወተትዋ ሳይጠቀም ወኪያ ሰጪው አይውሰድበት::

ለ. ምናልባት <u>ወኪያ</u> ሰጪው በተራው ተቸግሮ ወይም በሌላ በሆነ ምክንያት ወኪያ የተሰጠው ሰውዬ በአንድ ዙር ወተት ከመጠቀሙ በፊት ላሚትዋን ወይም ጥጃዋ ገና ሳትወልድ ከወሰደበት ወሳጁ ለተወሰደበት ሰውዬ ብር 100/አንድ መቶ ብር/ ካሣ ይከፈለው::

ሐ. ወኪያ የተሰጠው ሰው በአንድ ዙር ወተቱ ከተጠቀመ በኋላ ባለወኪያው ላሚትዋን ለመውሰድ ፈልጎና ጠይቆ አልሰጥም ካለ በጉራጌ ቂጫ መሠረት እንዲመልስ ይደረግ:: ወኪያ ሰጪውን በማጉላላቱ ብር 100 /አንድ መቶ ብር/ ተቀጥቶ ላሚትዋን ለባለቤቱ ይመልስ::

### 14.2 <u>ወዘም/ወንዘም</u>

ወዘም/ወንዘም ከወኪያ ሥርዓት የተለየ ስለሆነ በሁለቱ ተስማሚዎች/ተዋዋዮች መካከል በሚደረግ ስምምነት መሠረት ይፈጸም::

### 14.3 <u>ውኪየር</u>

ጉራጌ በባህሉ ቀን ሲሠራ ውሎ ምሽት ሲደርስ አካባቢው ወይም ጐረቤቶች ተገቢ ነው በሚሉት ሽማግሌ ቤት ወይም እንደ ሁኔታው በተራም ቢሆን ተሰባስበው ስለሥራቸው፣ ስለአካባቢያቸው፣ ስለአገርና ጠቅላላ ሁኔታዎች፣ ስለባህልና ታሪክ ወዘተ... የሚወያዩበት የሚጨዋወቱበትና የሚመካከሩበት ሥርዓት ስለሆነ ጠቀሜታውም ከፍ ያለ በመሆኑ ቂጫ ውስጥ ገብቶአልና አጠቃቀሙ ይቀጥል:: ሆኖም

ከፍተኛ ሰንጋ ገዝተው የበለጠ ከበሬታ ባለው አባል ቤት ወይም በወቅቱ በሚወስኑት አባል ቤት አርደው ሥጋውን ተካፍለው በዓሉን ያከብሩ ነበር:: የዚህም ጥቅሙ ተቀራርቦና ተከባብሮ መኖርን የመሰሉ በጎ ጐኖች ነበሩት:: በዛሬው ጊዜ ግን ሁኔታው ሙሉ በሙሉ ተለውጦ በአብዛኛው ቦታ ከማን አንሼ በማለት በየደጃፉ ጥጃዎችን ስለሚያርድ መሠረታዊ ባህሉ የተናጋ ከመሆኑም ባሻገር አድገው ጥጃ ሊወልዱ የሚችሉ፣ አድገው ለእርሻ ወይም ሰንጋ ሊሆኑ የሚችሉትን ጥጃዎችና ወይፈኖችን በብዛት በማረድ በዓሉን ያከብራል:: ይህ ጥጃዎችን በየቤቱ የማረድ አዲስ ባህል የጉራጌን ብቻ ሳይሆን የሀገሪቱንም ኤኮኖሚ የሚጎዳ መሆኑ ግንዛቤ ስለተወሰደ የጉራጌ ተወላጅ የሆነ ሁሉ በዚህ ጉዳይ ላይ በጥብቅ አስቦበት ጥጃዎችንና ወይፈኖችን ማረዱን ትቶ እንደቀድሞው ከፍተኛ ከብቶችን በጋራ አርዶ እንዲጠቀም ተወስኖአል::

## አንቀጽ አሥራ አራት

## 14. <u>ማህበራዊ መተጋገዞች</u>

14.0 ማህበራዊ መተጋገዞች ብዛታቸው ከፍ ያለ ስለሆነ ዝርዝር ጥቅምና ጉዳታቸው ወደፊት የሚጠና ቢሆንም በተለይ <u>ወኪያን</u> በሚመለከት በቑጫው በግልጽ እንዲታይ ተደርጓል::

### 14.1 <u>ወኪያ</u>

ሀ. በጉራጌ ባህል ወኪያ ከብት ያለው ወይም በኑሮው ሻል ያለ ሰው በኑሮው ዝቅ ባለ ደረጃ የሚገኘው ሰው ኑሮውን ማቋቋም እንዲረዳው የሚያደርግ የተቀደሰ የመተጋገዣ ሥርዓት ነው:: በአሁኑ ጊዜ አንዳንድ ከብት ወኪያ የተሰጣቸው ሰዎች ከዚህ በፊት ያልነበረ ክህደት





ወይም ክርክር ስለፈጠሩ በመተጋገዣ ሥርዓቱ ላይ ችግር እንዳስከተለ ታውቆአል:: ስለዚህ ሤራ ሊወጣለት ይገባል:: <u>ቑጫውም</u> <u>ከብት ወኪያ</u> የተሰጠው ሰው ጥጃዋ ወልዳ ቢያንስ በአንድ ዙር ወተትዋ ሳይጠቀም ወኪያ ሰጪው አይውሰድበት::

ለ. ምናልባት <u>ወኪያ</u> ሰጪው በተራው ተቸግሮ ወይም በሌላ በሆነ ምክንያት ወኪያ የተሰጠው ሰውዬ በአንድ ዙር ወተት ከመጠቀሙ በፊት ላሚቱዋን ወይም ጥጃዋ ገና ሳትወልድ ከወሰደበት ወሳጁ ለተወሰደበት ሰውዬ ብር 100/አንድ መቶ ብር/ ካሣ ይክፈለው::

ሐ. ወኪያ የተሰጠው ሰው በአንድ ዙር ወተቱ ከተጠቀመ በኋላ ባለወኪያው ላሚትዋን ለመውሰድ ፈልጎና ጠይቆ አልሰጥም ካለ በጉራጌ ቑጫ መሠረት እንዲመልስ ይደረግ:: ወኪያ ሰጪውን በማጉላላቱ ብር 100 /አንድ መቶ ብር/ ተቀጥቶ ላሚትዋን ለባለቤቱ ይመልስ::

### 14.2 <u>ወዘም/ወንዘ</u>

ወዘም/ወንዘ ከወኪያ ሥርዓት የተለየ ስለሆነ በሁለቱ ተስማሚዎች/ተዋዋዮች መካከል በሚደረግ ስምምነት መሠረት ይፈጸም::

### 14.3 <u>ውኪየር</u>

ጉራጌ በባህሉ ቀን ሲሠራ ውሎ ምሽት ሲደርስ አካባቢው ወይም ጐረቤቶች ተገቢ ነው በሚሉት ሸማግሌ ቤት ወይም እንደ ሁኔታው በተራም ቢሆን ተሰባስበው ስለሥራቸው፣ ስለአካባቢያቸው፣ ስለአገርና ጠቅላላ ሁኔታዎች፣ ስለባህልና ታሪክ ወዘተ... የሚወያዩበት የሚጨዋወቱበትና የሚመካከሩበት ሥርዓት ስለሆነ ጠቀሜታውም ከፍ ያለ በመሆኑ ቑጫ ውስጥ ገብቶአልና አጠቃቀሙ ይቀጥል:: ሆኖም

ውኩየር የአልኮሆል መጠጫና የጫት መቃሚያ መድረክ መሆን የለበትም።

## 14.4. ማዞያ/ቀራት

ጉራጌ በባህሉ አካባቢውን በማዞያ/በቀራት ሲጠብቅ ኖሮአል። ይኸውም ሕብረተሰቡ ወር ተራ ገብቶ የአካባቢውን ጥበቃ የሚያካሂድበት ሥርዓት ነው። ማዞያ/ቀራት ሌብነትን የሚያጠፋ፣ የጉጂ አውሬዎችን ጥፋት የሚቀንስ፣ ሌሎች አደጋዎችና ጥፋቶችን የሚያስቀር የፀጥታ ማስከበሪያ ሥርዓት ስለሆነ ማዞያ/ቀራት ተጠናክሮ እንዲቀጥል በቋጫ ውስጥ ገብቶአል።

## 14.5 ዕድርና ዕቁብ

ዕድርና እቁብም ለፈጣሪያቸው ለጉራጌ ብሔረሰብ ብቻ ሳይሆን ለመላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ግልጋሎት እየሰጡ ናቸው። በተለይ በጉራጌ ክልል ደግሞ ለልማት ሥራዎች በድጋፍ ሰጪነት ከፍተኛ ሚና የተጫወቱና የሚጫወቱ በመሆኑ ሁለቱም የልማት ማንቀሳቀሻ ሞተሮች መሆን እንዲችሉ ያልተቆጠበ ጥረት ይደረግ።

## አንቀጽ አስራ አምስት

## 15. ማኅበራዊ ከበሬታዎች

### 15.1 እጀቦችና እጭኻደረት

ማኅበራዊ ከበሬታዎች ወደፊት በዝርዝር የሚጠኑ ቢሆኑም እንደ እጀቦች፣ እጭኻደረት ወዘተ... የመሳሰሉት በነበረው ሁኔታ ቢቀጥሉ የሚደገፍ ነው። ሆኖም በአንዳንድ ቦታ ሙሽሪት ወላጆችዋ ዘንድ ሆና የወለደች እንደሆነ ለአራስ ተብሎ ከአቅም በላይ የሆነ ወይፈንና ላም ከፍተኛ ወጪ ይጠየቃል የተባለው ተወግዞ እንዲቀር ተወስኖአል።





### 15.2 የሴቶች በዓል አከባበር

#### 15.2.1 አንትሮሽት

አንትሮሽት ከጥንት ተያይዞ የመጣ ከጉፑዋር ጋር የሚከበር የእናቶች በዓል ስለሆነ የእናቶች ቀን ተብሎ ከነበረው ተሻሽሎ ይቀጥል።

#### 15.2.2 ነቄ

የነቄ /የስንቻ በዓል አሁንም ይከበራል። ነቄ በዓመት አንድ ጊዜ ለአንድ ሣምንት የሚከበር የሴቶች ልጆች በዓል ነው። ከዚህ በፊት የነበረው አስጊው ልምድ ቀርቶ አሁን ባለው ሁኔታ ይቀጥል።

#### 15.2.3 ሣ፹ር

ሣ፹ሮ እናቶች ስምንተኛና አሥረኛ ልጃቸውን ሲወልዱ የተለየ የግል በዓል የሚያከብሩበት ሥርዓት ስለሆነ ለዚያ የሚደርሱ ካሉ ለጊዜው በነበረው አኳኋን ይከበር።

### 15.3 ባህላዊ የማዕረግ ስም አሰጣጥ

15.3.1 የጉራጌ ባህላዊ የማዕረግ ስም አሰጣጥ ሥርዓት አለው። የማዕረግ ስም የሚሰጠው ሰው በማህበረሰቡ ውስጥ በፈጸማቸው አስመስጋኝ ሥራዎች ላይ ተመሥርቶ የሕዝቡን ስሜት በተከተለ ሁኔታ የሰውየው ጥሸና አካባቢ ወዘተ... ካረጋገጠለት በኋላ ነበር። ዛሬ ግን ባህላዊ የማዕረግ ስም የሚሰጠው ምንም ዓይነት ሥርዓት በሌለው አኳኋን በመጠጥ፣ በጓደኝነት፣ ከማን አንሼ በማለት ወዘተ... እየሆነ መሄድ ስለሚታይበት እንዲታረም ተደንግጉአል።

15.3.2 ስለስሞቹ ዝርዝር ትርጉምና ደረጃን በተመለከተ ከጊዜው ጋር ተስተካክሎ በሚያገለግል ሁኔታ ዝርዝር ጥናት ተደርጎ ውጤቱ ለወደፊቱ በቺጫ ውስጥ ይግባ::

15.3.3 ከእንግዲህ ወዲያ የጉራጌ የባህል የማዕረግ ስም የሚሰጠው ሰው ሁሉ በቤተሰብ፣በገኘ፣ በጥቭና በአካባቢ ሽማግሌዎች ተጣርቶና ተገምግሞ ከተግባሩ ጋር የተመጣጠነ ስም ሊሰጠው ይገባል:: ደረጃውም እንደዚሁ ተገምግሞ ሕዝብ አምኖበት የሚቀበለው መሆን አለበት:: በዘፈቀደ የሚሰጠው ስም ይቁም:: ስሞችም ከጦርነት ጋር ብቻ ማያያዝ ሳይሆን በልማት ሥራዎች፣ በማህበራዊ አገልግሎቶች፣ በቸርነት፣ ለችግር ጊዜ በመድረስ፣ ፍትሕ በመጠበቅ፣ በዕድሜ ወዘተ... በሚያበረክቱት ግልጋሎቶች መመሥረት አለበት::

15.3.4 ይህ ሥርዓት ከመውጣቱ በፊት አላግባብ የተሰጡ የጉራጌ የባህል የማዕረግ ስሞች ካሉና ባለቤቱ እኔ ለዚህ ደረጀ ሣልደርስ የተሰጠኝ ስም ስለሆነ ይነሳልኝ ወይም ይለወጥልኝ ካለ ጉዳዩ በሚመለከታቸው ሽማግሌዎች ተገምግሞ እርማት ማድረግ ይቻላል::



ምዕራፍ አምስት

## የቤት አሠራር፣ የጀፎረ፣ የቂየ/የዳር፣ የሞጣ፣ የባህላዊና የሠረጌ ቦታዎች

## አንቀጽ አሥራ ስድስት

### 16.1 የቤት አሠራር

ጉራጌ በአካባቢው የቤት አሠራር ዘዴና በጋራ የሚጠቀምባቸው ቦታዎች አስተዳደር የሚመለከቱ ሤራዎች አሉት:: የጉራጌ ቴክኖሎጂ ባህልን በተመለከተ የቤት አሠራር ጥሩ ሆኖ ሳለ የነፋስና የብርሃን መግቢያ መስኮት ስለማይኖረው መስኮት እንዲኖረው ጥረት ይደረግ፤ እንደዚሁም ሌሎችም ገምቢ የሆኑ ማሻሻያዎች ካሉ ይታከሉበት::

### 16.2 ቂየ

የባለቦታዎችን መሬት ከጀፎረ፣ ከመንገድና ከሌሎች ባለቦታዎች መሬት የሚለየው ቂየ የወሰን ድንጋይ በጉራጌ ባህል የተከበረ ነው:: ስለዚህ ቂየ/ የወሰን ድንጋይ በቀንም ሆነ በሌሊት የነቀለ ሰው ብር 500 /አምስት መቶ ብር/ ቅጣት ከፍሎ ድንጋዩን ወደነበረበት ይመልስ:: በአፈጻጸሙም አለመተማመን ከተከሰተ በ5 ሉካዎች አማካይነት ሙሪ በመጥራት ይፈጸም::

### 16.3 ጀፎረ

በጉራጌ ባህል የጀፎረ አከላለልና አጠባበቅ ሥርዓት ነበረው፤ አለውም:: ዳሩ ግን በአሁኑ ጊዜ በብዙ ቦታ ሤራው እየተጣሰ አጥር ይታጠራል፤ ቤት ይሠራበታል፤ አትክልት ይተከልበታል፤ ዛፍ ይተከልበታል፤ እነዚህ ሁሉ ከጉራጌ ሤራ ውጪ የሚፈጸሙ ናቸው:: አገልግሎቱ ለጋራ ስለሆነ የጀፎረ ሥርዓት መከበር አስፈላጊነት ሁሉም አምኖበታል:: ስለዚህ በየክፍለ-ሕዝቡ ጥንት በነበረው ሁኔታ እንዲከበር ይደረግ:: የጀፎረ ጉዳይ የሚወሰነው

በተጠቃሚው ጠቅላላ ሕዝብ እንጂ በአንድ ተገልጋይ ብቻ አይደለም፡፡

**16.4 ሞጣ/ዋድ/ወገርዴማ**

ሞጣ/ዋድ/ወገርዴማ የተባሉት የሕዝብ መተላለፊያ መንገዶች ናቸው፤ በአንዳንድ ቦታ እየተዘጉ ስለሆነ በነበረው ባህል መሠረት ሳይዘጉ ሕዝብ እንዲገለገልባቸው ይደረግ፡፡

**16.5 የባህልና የሠረጌ ቦታዎች አጠባበቅና አጠቃቀም**

የባህላዊና የሠረጌ ቦታዎች አጠበባቅና አጠቃቀምን በሚመለከት እስከአሁን ባሉ የባሕልና የሰረጌ ቦታዎች አጠባበቅና አጠቃቀም ባህል መሠረት ተጠብቀው ሕብረተሰቡ ቦታዎቹ በተያዙባቸው/በተያዙላቸው ዓላማዎች መሠረት ለሕዝቡ ግልጋሎት ላይ እንዲውሉ ይደረግ፤ ወደፊትም በዚሁ መሠረት ይቀጥል፡፡









## ምዕራፍ ስድስት

## ባሕላዊ ሕክምና፣ አካል ማሠልጠኛ፣ ስፖርትና ኪነት

አንዳንድ ኋላቀር የሆኑ አሠራሮችና አጠቃቀሞችን በማሻሻልና ጥንቃቄ በመውሰድ ባሕላዊ ሕክምናዎች፣ ያካል ማሠልጠኛዎች፣ ስፖርትና ኪነት ሕዝቡን የሚጠቅሙ በመሆናቸው ተጠናክረው በተግባር መዋላቸው መቀጠል አለበት፡፡

### አንቀጽ አሥራ ሰባት

**17.1 ባህላዊ ሕክምና**

17.1.1 በባህላዊ አምልኮ ሕክምናዎች ከመጠቀም በፊት በተቻለ መጠን፣ ኅብረተሰቡ በዘመናዊ ሕክምና እንዲጠቀም ማበረታታት ይገባል፡፡

17.1.2 የባህል ሕክምና ሰጪዎችና መርፌ ወጊዎች «በሚያክሙበት» ወቅት መጠጥ በመውሰድ በአደገኛ ሁኔታ «ያክማሉ» ስለሚባል በእንደዚህ ያለ ሁኔታ «የሚያክሙ» ቢኖሩ ክትትል ተደርጎ «እንዳያክሙ» ማድረግ ይገባል፡፡

17.1.3 በባህላዊው ሕክምና ሂደት ሰው ቢሞት ወይም የአካል መጉደል ቢከሰት ጉዳቱ የደረሰው በእርግጥ በዚህ ምክንያት መሆኑ ከተረጋገጠ «አካሚው/ዋ» በደም ወይም በአካል ጉድለት ሜራ ይጠየቅ/ትጠየቅ፡፡

17.1.4 ከፍተኛ ሙያ ያላቸው የአጥንት ስብራት፣ የወለምታና ሌሎችም የባህል ሕክምና የሚሰጡ ዕውቅ የልምድ የሕክምና ባለሙያዎችና የልምድ አዋላጆች ለህብረተሰቡ ጠቃሚ የሆነ የሕክምና አገልግሎት በመስጠት ላይ እንደሚገኙ ይታወቃል፡፡ ሆኖም አሠራራቸውና መድኃኒት አሰጣጣቸው በህብረተሰቡ ጤና ላይ አደጋ እንዳያስከትል

የጤና ትምህርት ቀስመው በብርቱ ጥንቃቄ አገልግሎታቸውን እንዲቀጥሉ እንዲደረግ ተወስኖአል::

17.1.5 ኤድስ ፍጹም አደገኛ በመሆኑ ሁሉም የኅብረተሰብ አካላት የመከላከያ ትምህርት የሚያገኙበት ሥርዓት እንዲዘረጋ ተወስኖአል::

17.1.6 የኤድስ በሽተኛ መሆኑን አውቆ ሆነ ብሎ ሌላውን ሰው በክሎ የኤድስ ተጠቂ ያደረገ ሰው ሁኔታው በሚገባ ተጣርቶና ተገምግሞ በደረጃ በነፍስ ግድያ ሜራ መሠረት ይጠየቅ:: ሌሎችንም በተጋቦት የሚተላለፉ ጠንቀኛ በሽታዎችን ሆን ብሎ ወደ ሌላ ወገን ያስተላለፈ ሁኔታው እየተጣራ እንደየጥፋት ደረጃው ይጠየቅ::

17.1.7 ሲጃራ ማጨስ ለጤና አደገኛ መሆኑ ታውቆ ሰዎች ሲጃራ ባለማጨስ ጤናቸውን እንዲጠብቁ ብርቱ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል:: በስብሰባ ወቅትና ቦታ ሲጃራ ማጨስ ፍጹም የተከለከለ ነው::

## 17.2 አካል ማሠልጠኛና ስፖርት

17.2.1 በጉራጌ ባህል ውስጥ መበረታታት ያለባቸው ስፖርቶች ብዙ ናቸው:: ያለባቸው ድክመት ታርሞ በተሻሻለ ሁኔታ መቀጠል አለባቸው:: ለምሣሌም ያህል ቁየ/የገና ጨዋታ ይጠቀሳል::





### 17.2.2 ቁየ

ሀ. የአጨዋወት ሥርዓት ይኑረው::

ለ. የሚመራ ዳኛ ይኑረው::

ሐ. ኳሱ የሩር መሆኑ ቀርቶ ከቃጫ የተዘጋጀ ይሁን::

መ. ሌሎችም ጉዳት የሚያመጡ ችግሮች ቢኖሩ ታርመው አደጋ በማያደርሱ ሁኔታ የገና ጨዋታ ይቀጥል:: የጉግሥም ጨዋታ እንደዚሁ ያለበት ድክመት ታርሞ ይቀጥል:: ሌሎችም እየተጠኑ ግልጋሎት ላይ የሚውልበት ሁኔታ እንዲመቻች ተወስኖአል::

## 17.3 ኪነጥበብና ኪነት

17.3.1 በጉራጌ ባህል በዘፈን፣ በበድራ፣ በወየግ ወዘተ.. መልክ ማህበራዊ ክበሬታዎች እንዲዳብሩ በአንፃሩም ማህበራዊ ነውሮች እንዲከስሙ፣ አባትና እናት ልጆቻቸውን የሚንከባከቡበትን፣ ልጆችም አባትና እናታቸውን የሚያከብሩበትንና የሚጦሩበትን፣ የልማት ሥራዎች የሚጠናከሩበትን መንገድ ሊከፍት የሚያስችል ጉዳና ስለሆነ ኪነት እንዲዳብር በጥናት እየተደገፈ ይስተግበር::

17.3.2 ጉራጌ ልዩ ልዩ ባህል ጨዋታዎችና ኪነጥባባት ያሉት ስለሆነ በተለያየ መልካቸው ተሰብስበውና ተጠንተው ሕይወት ሊዘሩ በሚችሉበት ሁኔታ እንዲቀረጹ፤ ከዚህ በፊት ጉሕራልድ ያሰባሰባቸው የባህል ዘፈኖችና በቪዲዮ የተቀረጹ ትርዕይቶች ሁሉ ተሰባስበው አብረው እየተጠኑ ይሠራባቸው::

## በንብረት ላይ ጉዳት ማድረስ የሚያስከትለው እርምጃ

### አንቀጽ አሥራ ስምንት

በጉራጌ ባህል በሰው ንብረት ላይ ሆነ ተብሎ ጉዳት ማድረስ የተወገዘ ድርጊት ነው:: በርቸ እንዳይሆን ጥንቃቄ ይደረጋል::

#### 18.1 የቤት ቃጠሎ

18.1.1 በግፍ ቤት ያቃጠለ ሰው ቤቱ ለተቃጠለበት ወገን ብር 20,000/ሃያ ሺህ ብር/ ይከፍላል::

18.1.2 የቤቱ ቃጠሎ በመዳራ/በስህተት ባለማወቅ ሲሆን አቃጣዩ ቤቱ ለተቃጠለበት ሰው ብር 10,000/አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

18.1.3 የቤቱ ቃጠሎ በመዳራ መዳራ/የስህተት ስህተት ሲሆን አቃጣዩ ቤቱ ለተቃጠለበት ሰው ብር 5,000/አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

18.1.4 እንስሳትና የቤት ቆሳቁስ ከተቃጠሉ ዋጋቸው ተገምቶ አቃጣዩ ለተቃጠለበት ሰው በተጨማሪ ይከፍላል::

18.1.5 በቃጠሎው አንድ ሰው ወይም ከአንድ ሰው በላይ ሕይወት ከጠፋ በሰው ግድያ ወንጀል ሜራ መሠረት በእያንዳንዱ ሰው በየደረጃው ይጠየቃል::

18.1.6 በቃጠሎ አንድ ሰው ወይም ከአንድ ሰው በላይ የአካል መጉደል ከደረሰ በአካል ማጉደል ወንጀል ሜራ መሠረት በእያንዳንዱ ሰው በየደረጃው ይጠየቃል::

18.1.7 አንድ እብድ ሰው ቤት ካቃጠለ ዘመዶቹ ቤት ለተቃጠለበት ሰው አንድ ጤነኛ ሰው ቤት





ሲያቃጥል በዚህ ሜራ መሠረት ሊከፍል ከሚገባው ካሣ 1/6ኛ /ከስድስት አንድ እጅ/ይከፈሉ:: ከሰውም ሆነ ከእንስሳት ሕይወት መጥፋትና ከንብረት መውደም ጋር የተያያዘ ሁኔታ ከተፈጠረም በየደረጃው ይጠየቁ::

#### 18.2 የሰብል ማቃጠል፣ መንቀልና መቁረጥ ወንጀል

18.2.1 ማናቸውም ሰው በቂም በቀልና ፍትሕ ተጓደለብኝ ወይም ተበደልኩ በማለት ሰብልን/አዝርዕትን፣ ቡና፣ እሰት፣ ጫትና ባሕርዛፍ ወዘተ... ማቃጠል፣ መንቀል፣ ወይም መቁረጥ የተወገዘ ድርጊት ነው::

18.2.2 ተበደልኩ የሚል ግለሰብ ወይም ቡድን በደሉን በየደረጃው ለሚገኙ የሜራ አስፈጻሚዎች አቅርቦ ማስወሰንና ማስፈጸም አለበት:: በዚህ መሠረት ሳያስፈጽምና የሽማግሌዎችን ውሳኔ ሳያገኝ በሰብል ላይ ጉዳት ያደረሰ ሰው:-

ሀ. ጥፋት በመፈጸሙ ከብር 30-5,000/ከሰላሳ እስከ አምስት ሺህ ብር/ ቅጣት ይከፍላል::

ለ. ያጠፋው ሰብል በሽማግዎች ተገምቶ ለባለንብረቱ ይከፍላል::

# ምዕራፍ ስምንት

## ሥርቆት

### አንቀጽ አሥራ ዘጠኝ

19.0 ሌብነት በጉራጌ ባህል የተወገዘ ድርጊት ስለሆነ ሌብነት እንዲጠፋ የሁሉም ሰው ያልተቆጠበ ጥረት መኖር አለበት::

19.1 <u>የቀንድና የጋማ ከብት ሥርቆት</u>

የቀንድና የጋማ ከብት የሠረቀ ለጥቆማ የወጣ ሂሳብ ካለ በተለይ ክፍሎ ከብር 50-2,000 /ከሃምሣ እስከ ሁለት ሺህ ብር/ መቀጫ ይከፍላል:: ከብቶቹንም ለባለንብረቱ ይመልሳል:: ከብቶቹን መመለስ ካልቻለ በሽማግሌ በተገመተ የገበያ ዋጋቸው ለባለንብረቱ ይከፍላል ወይም መሰል ከብት ይተካል::

19.2 <u>የሰብል/የእርሻ ውጤቶች ሥርቆት</u>

ሰብል፣ የእርሻ ውጤቶችን የሠረቀ ለጥቆማ የወጣ ሂሣብ ካለ በተለይ ክፍሎ በመሥረቁ ከብር 50-2,000/ከሃምሣ እስከ ሁለት ሺህ ብር/ መቀጫ ይከፍላል:: የሰረቀውን እህልም በነበረበት ሁኔታ ለባለንብረቱ ይመልሳል፤ መመለስ ካልቻለም የሰብሉ ዋጋ በሽማግሌ ተገምቶ ለባለንብረቱ ይከፍላል::

19.3 <u>የእምነት ቦታዎችን በመድፈር ንብረት የሠረቀ</u>

19.3.1 የእምነት ቦታዎች ንብረቶችን የሠረቀ ሌባ የሠረቃቸውን ንብረቶች ሁሉ ለባለንብረቱ ይመልስ::

19.3.2 ንብረቶቹ በሥውር ቦታ የተደበቁ ከሆነም ሌባው መርቶ ያሳይ::





19.3.3 የተሠረቁ እቃዎችን መመለስ ወይም ያሉበትን ቦታ መርቶ ማሳየት ካልቻለ የንብረቶቹን ዋጋ በሽማግሌዎችና በባለሙያዎች ተገምቶ ለባለንብረቱ ይከፈል::

19.3.4 ሌባው ለፈጸመው ድርጊት ከብር 10,000-50,000/ ከአሥር ሺህ እስከ ሃምሣ ሺህ ብር/ መቀጫ ይከፈል::

19.4 <u>የማኅበራዊና የኤኮኖሚ አገልግሎት ተቋሞችን ንብረት የሰረቀ</u>

የትምህርት ቤቶች፣ የሆስፒታሎች፣ የክሊኒኮች፣ የሕዝባዊ ድርጅቶች ወዘተ... ንብረት ደፍሮ የሰረቀ ሰው፣

ሀ. ንብረቶቹን በሙሉ ለባለንብረቱ መመለስ አለበት::

ለ. ንብረቶቹን ካልመለሰ ዋጋቸው በሽማግሌና በባለሙያ ተገምቶ ለባለንብረቱ መክፈል አለበት::

ሐ. ለፈጸመው ጥፋትና ድፍረት ከብር 5,000-50,000 /ከአምስት ሺህ እስከ ሃምሣ ሺህ ብር/ መቀጫ ይከፈል::

### አንቀጽ ሃያ

20. <u>ኧፈንገይነት/የሌብነት ሉካዎች እና የሌባ ተቀባይ</u>

20.1 <u>የሌብነት ሉካዎች</u>

20.1.1 የጋማ ከብት የተሰረቀበት ሰው ሰረቀኝ ብሎ የጠረጠረው ሰው ከሉካዎቹ ዘጠኝ ቆጥሮ ሙሪ ይጠራል::

20.1.2 የቀንድ ከብት የተሰረቀበት ሰው ሰረቀኝ ብሎ የጠረጠረው ሰው ከሉካዎቹ ሰባት ቆጥሮ ሙሪ ይጠራል::

20.1.3 በግና ፍየል የተሰረቀበት ሰው ሰረቀኝ ብሎ የጠረጠረው ሰው ከሉካዎቹ አምስት ቆጥሮ ሙሪ ይጠራል::

20.1.4 ሰብል የተሰረቀበች ሰው ሰረቀኝ ብሎ የጠረጠረው ሰው ከሉካዎቹ አምስት ቆጥሮ ሙሪ ይጠራል::

20.1.5 የእምነት ቦታዎች ንብረት የተሰረቀበት ሰው ወይም ድርጅት ሰረቀኝ ብሎ የጠረጠረው ሰው ወይም ሰዎች ከ5-12 የትውልድ ሐረግ ቆጥሮ ከሉካዎቹ ውስጥ 24 ሙሪ ይጠራል::

## 20.2 የሌባ ተቀባይ

የሌባ ተቀባይም ጥፋተኛ ስለሆነ ሌባው በሚከፍለው መቀጫ መጠን ይከፍላል::







# ምዕራፍ ዘጠኝ

## የአልኮሆል መጠጥና ጉጂ ዕጾች

### አንቀጽ ሃያ አንድ

## 21.1 አልኮሆል

21.1.0 የአልኮሆል መጠጥ ከዚህ በታች በተዘረዘሩ ቦታዎችና ጊዜዎች መጠጣት የተወገዘ መሆኑ በጉራጌ ባህላዊ ሸንጎዎች ሁሉ ምክር እንዲሰጥበት ሆኖ በቂጫ ደረጃ የተወሰኑትን እንዲያከብር ጥሪ እንዲደረግ ተወስኖአል::

21.1.1 እርሻ በሚታረስበት ወቅት፣ ቦታና አካባቢው፤

21.1.2 ሽምግልናና ዳኝነት በሚታይበት ወቅት በሸንጎና አካባቢው፤

21.1.3 ቤት በሚሠራበት ጊዜ በቦታውና በአካባቢው፤

21.1.4 ሰው ሞቶ ቀብርና ለቅሶ በተቀመጡበት ጊዜ፣ቦታና አካባቢው፣

21.1.5 ሴት የማጨት ጥያቄ ቀርቦ በሚወያዩበትና የመተጫጨት ሥርዓት በሚፈጸምበት ወቅትና ቦታ፣

21.1.6 ሴቶች እሰት በሚፍቁበት ቦታና ጊዜ አልኮሆል መጠጣት የተከለከለ ነው::

21.1.7 በእነዚህ ቦታዎችና ወቅቶች አረቄ ያቀረበ ወይም የጠጣ የገንዘብ ቅጣትና መሐላ አለበት:: የገንዘቡ ቅጣትም (ከመሐላው መጣስ ጋር) ብር 100 ይከፍላል::

21.1.8 አረቄ በተዝካርም ሆነ ለቤተክርስቲያን ለቁርባን ድግሥ መቅረብ የለበትም፤ ተከልክሎአል::

21.2 ጫ ት

21.2.0 ጫት መብላት/መቃም እንደ አረቂ በጉራጌ ኅብረተሰብ ላይ ከፍተኛ ጉዳትና ችግር ያደረሰ መሆኑ የተረጋገጠ ነው:: ስለዚህ:-

21.2.1 እርሻ በሚታረስበት ወቅት በቦታውና በአካባቢው፣

21.2.2 ቤት በሚሠራበት ጊዜ በቦታውና በአካባቢው፣

21.2.3 ሽምግልናና ዳኝነት በሚታይበት ወቅት በሸንጎችና አካባቢያቸው፣

21.2.4 ሰው ሞቶ ቀብርና ለቅሶ በተቀመጡበት ጊዜ ቦታና አካባቢው፣

21.2.5 ሴት የማጨት ጥያቄ ቀርቦ በሚወያዩበትና የመተጫጨት ሥርዓት በሚፈጸምበት ወቅትና ቦታ፣

21.2.6 ሴቶች እሰት በሚፍቁበት ቦታና ጊዜ ጫት መብላት/መቃም የተወገዘ ነው::

21.2.7 ጫት ያቀረበ ወይም የበላ/የቃመ ቅጣትና መሐላ አለበት:: የገንዘቡ ቅጣትም ብር 100 /አንድ መቶ ብር/ ነው:: ሆኖም በእስልምና ሃይማኖት ብቻ ለቅሶ በተቀመጡበት ቦታ ለዱአ የሚያስፈልግ መሆኑ ከታመነበት ይህ ሂራ አይመለከተውም::

21.3 ሌሎች ጉጂ ዕጾች

በሌሎች ጉጂ ዕጾች በማናቸውም ቦታና ጊዜ መጠቀም የተወገዘ በመሆኑ ኅብረተሰቡ እየተከታተለ ማኅበራዊ እርምጃ እንዲወስድ ተወስኖአል::



## ምዕራፍ አሥር

### አካል ማጉደል

#### አንቀጽ ሃያ ሁለት

በጉራጌ ባህል የሰውን አካል ማጉደል ከባድ ወንጀል ነው::

22.1 ዓይን ማጥፋት

22.1.1 አንድ ዓይን ያጠፋ የሕክምና ወጪን ችሎ ብር 10,000.00/አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.1.2 ሁለት ዓይን ያጠፋ የሕክምና ወጪን ችሎ ብር 25,000.00/ሃያ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.2 ጥርስ መስበር

በደረሰው አደጋ ምክንያት የወጣ የሕክምና ወጪን ሸፍኖና ጥርስም አስተክሎ ጥርስ ሰባሪው ጥርሱ ለተሰበረበት ሰው ከብር 1,000 እስከ 3,000 /ከአንድ ሺህ እስከ ሦስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.3 ጆሮ ማደንቆር

22.3.1 አንድ ጆሮ ያደነቆረ ሕክምናውን ችሎ ብር 2,500 /ሁለት ሺህ አምስት መቶ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.3.2 ሁለት ጆሮ ያደነቆረ ሕክምናውን ችሎ ብር 7, 500.00/ሰባት ሺህ አምስት መቶ ብር/ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.4 ጆሮ መቁረጥ

22.4.1 አንድ ጆሮ የቆረጠ ሕክምናውን ችሎ ከብር 500-2000 /ከአምስት መቶ እስከ ሁለት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

21.2 ጫ ት

21.2.0 ጫት መብላት/መቃም እንደ አረቂ በጉራጌ ኅብረተሰብ ላይ ከፍተኛ ጉዳትና ችግር ያደረሰ መሆኑ የተረጋገጠ ነው:: ስለዚህ:-

21.2.1 እርሻ በሚታረስበት ወቅት በቦታውና በአካባቢው፣

21.2.2 ቤት በሚሠራበት ጊዜ በቦታውና በአካባቢው፣

21.2.3 ሽምግልናና ዳኝነት በሚታይበት ወቅት በሸንጎችና አካባቢያቸው፣

21.2.4 ሰው ሞቶ ቀብርና ለቅሶ በተቀመጡበት ጊዜ ቦታና አካባቢው፣

21.2.5 ሴት የማጬት ጥያቄ ቀርቦ በሚወያዩበትና የመተጫጬት ሥርዓት በሚፈጸምበት ወቅትና ቦታ፣

21.2.6 ሴቶች ኧሰት በሚፍቁበት ቦታና ጊዜ ጫት መብላት/መቃም የተወገዘ ነው::

21.2.7 ጫት ያቀረበ ወይም የበላ/የቃመ ቅጣትና መሐላ አለበት:: የገንዘቡ ቅጣትም ብር 100 /አንድ መቶ ብር/ ነው:: ሆኖም በእስልምና ሃይማኖት ብቻ ለቅሶ በተቀመጡበት ቦታ ለዱአ የሚያስፈልግ መሆኑ ከታመነበት ይህ ሤራ አይመለከተውም::

21.3 ሌሎች ጉጂ ዕጾች

በሌሎች ጉጂ ዕጾች በማናቸውም ቦታና ጊዜ መጠቀም የተወገዘ በመሆኑ ኅብረተሰቡ እየተከታተለ ማኅበራዊ እርምጃ እንዲወስድ ተወስኖአል::



ምዕራፍ አሥር

አካል ማጉደል

አንቀጽ ሃያ ሁለት

በጉራጌ ባህል የሰውን አካል ማጉደል ከባድ ወንጀል ነው::

22.1 ዓይን ማጥፋት

22.1.1 አንድ ዓይን ያጠፋ የሕክምና ወጪን ችሎ ብር 10,000.00/አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.1.2 ሁለት ዓይን ያጠፋ የሕክምና ወጪን ችሎ ብር 25,000.00/ሃያ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.2 ጥርስ መስበር

በደረሰው አደጋ ምክንያት የወጣ የሕክምና ወጪን ሸፍኖና ጥርስም አስተክሎ ጥርስ ሰባሪው ጥርሱ ለተሰበረበት ሰው ከብር 1,000 እስከ 3,000 /ከአንድ ሺህ እስከ ሦስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.3 ጆሮ ማደንቆር

22.3.1 አንድ ጆሮ ያደነቆረ ሕክምናውን ችሎ ብር 2,500 /ሁለት ሺህ አምስት መቶ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.3.2 ሁለት ጆሮ ያደነቆረ ሕክምናውን ችሎ ብር 7, 500.00/ሰባት ሺህ አምስት መቶ ብር/ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.4 ጆሮ መቁረጥ

22.4.1 አንድ ጆሮ የቆረጠ ሕክምናውን ችሎ ከብር 500-2000 /ከአምስት መቶ እስከ ሁለት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.4.2 ሁለት ጆሮ የቆረጠ ሕክምናውን ችሎ ከብር 2,000-5,000 /ከሁለት ሺህ እስከ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.5 እጅ መቁረጥ

22.5.1 አንድ እጅ የቆረጠ የሕክምና ወጪውን ችሎ ብር 10,000 /አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.5.2 ሁለት እጅ የቆረጠ የሕክምና ወጪውን ችሎ ብር 25,000 /ሃያ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.6 እግር መቁረጥ

22.6.1 አንድ እግር የቆረጠ የሕክምና ወጪውን ችሎ ብር 10,000 /አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.6.2 ሁለት እግር የቆረጠ የሕክምና ወጪውን ችሎ ብር 25,000 /ሃያ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.7 አፍንጫ መቁረጥ

አፍንጫ የቆረጠ የሕክምና ወጪውን ችሎ ከብር 1,000-7,000 /ከአንድ ሺህ እስከ ሰባት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.8 ምላስ መቁረጥ

22.8.1 ምላሱ የተቆረጠ ሰው በዚሁ በምላሱ መቆረጥ ምክንያት መሞቱ ከተረጋገጠ ምላስ ቆራጩ በደም ሤራ መሠረት በየደረጃው ይጠየቃል::





22.8.2 ምላሱ የተቆረጠው ሰው ካልሞተ ምላስ ቆራጩ ማሳከሚያውን ችሎ ከብር 3,000-15,000 /ከሦስት ሺህ እስከ አሥራ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.9 ከንፈር መቁረጥ

ከንፈር የቆረጠ የሕክምና ወጪን ችሎ ከብር 5,000-10,000 /ከአምስት ሺህ እስከ አሥር ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.10 ጣት መቁረጥ

22.10.1 አውራ ጣት የቆረጠ ማሳከሚያውን ችሎ ብር 2,000 /ሁለት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.10.2 ሌሎች ጣቶችን የቆረጠ ማሳከሚያውን ችሎ በእያንዳንዱ ጣት ብር 1,000 /አንድ ሺህ ብር/ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.11 ራስ መፈንከት

22.11.1 ራስ የፈነከተ ሰው ተጎጂው ሰው ታክሞ የሚድን ከሆነ አደጋ አድራሹ የሕክምና ወጪውን ችሎ ከብር 200-2,000/ከሁለት መቶ እስከ ሁለት ሺህ ብር/ካሣ ለተጎጂው ይከፍላል::

22.11.2 በፍንከቱ ወይም በሌላ በማናቸውም በታወቀ ተመሳሳይ ምክንያት አንድ ሰው አዕምሮውን ከሣተ ጉዳት አድራሹ ለተጎጂው ከብር 15,000-25,000 /ከአሥራ አምስት ሺህ እስከ ሃያ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

22.11.3 አንድ ዕብድ ሰው የሌላውን ሰው አካል ካጎደለ ዕብድ መሆኑ በታወቀ ሐኪም መረጋገጡ






እንደተጠበቀ ሆኖ በአካል ማጉደል ሜራ መሠረት እንደሁኔታው በሽማግሌዎች ታይቶ ይወሰን:: በእጅ አዙር የሌላ ሰው መጠቀሚያ ከሆነ ግን በአካል ማጉደሉ ሜራ መሠረት በደረጃው ይጠየቅ::

## አንቀጽ ሃያ ሦስት

### 23. አባለዘር ማበላሸት

የወንድም ሆነ የሴት አባለዘር ያበላሸ የሕክምና ወጪውን ችሎ ብር 15,000 /አሥራ አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ለተጎጂው ወይም ለተጎጂዋ ይከፍላል::






# ምዕራፍ አሥራ አንድ

## ግድያ

## አንቀጽ ሃያ አራት

24.0. በጉራጌ ባህል ሰው ክቡር ፍጥረት ስለሆነ ግድያ እንዳይፈጸምበት ከፍተኛ የመከላከል ጥረት ይደረጋል:: ግድያ ከተፈጸመም በርቾ ሆኖ እንዳይቀጥል ደም በቈጫ ሥርዓት እንዲያልቅ ካልተደረገ የሚያስከትለው ውጤት መጥፎ እንደሚሆን ይታመናል::

### 24.1 ሙራ ደም/የግፍ አገዳደል

በሙራ ደም ሥርዓት ሰው በግፍ የገደለ ብር 30,000 /ሠላሣ ሺህ ብር/ የደም ካሣ መክፈል አለበት::

### 24.2 መዳራ

የመዳራ ግድያ ሲሆን ( በስህተት ግድያ ሲፈጸም) ገዳይ ብር 15,000 /አሥራ አምስት ሺህ ብር/ የደም ካሣ መክፈል አለበት::

### 24.3 ኧመዳራ መዳራ

ግድያው ኧመዳራ መዳራ ( በፍጹም በስህተት የተፈጸመ) ሲሆን ገዳይ ብር 7,500 /ሰባት ሺህ አምስት መቶ ብር/ የደም ካሣ ይከፍላል::

### 24.4 ሉካዎችን ሙሪ መጥራት

ለነፍስ ግድያ የዓይን ምስክር የጠፋ እንደሆነ ገዳይ ነው የተባለው ሰው ከራሱ ጀምሮ እስከ አምስት የትውልድ ሐረጉ ከዚያ ካልተገኘም እስከ አሥራ ሁለት የትውልድ ሐረጉ ድረስ ካሉ ዘመዶቹ ተበዳይ ወገን አሥራ ሁለት ሉካዎችን ሙሪ ጠርቶ/ቆጥሮ ያስምልና ከሦስቱ የግድያ ወንጀሎች በአንዱ ይጠየቃል::

24.5 የዘመዶች ገዳይን የማቅረብ ግዴታ

አንድም ሆነ ብዙ ሰዎች ሆነው ሰላማዊ ሰው ገድለው ቢያመልጡ ዘመዶቹ /ዘመዶቻቸው ይዘው ማቅረብ አለባቸው። ካላቀረቡ የገዳዩ/ የገዳዮቹ የአያት ልጆች ቤታቸውን ዘግተው ይወጣሉ። ቤታቸውን ለቀው ከወጡ በኋላ ሽማግሌ ልከውና ለእርም ማውጫ /ለእምባ/ ብር 3,000 (ሦስት ሺህ ብር) በቅድሚያ ከፍለው ወደ ቀያቸው ይመለሳሉ። ይህም ሂሣብ ገዳዩ በቺጫ መሠረት ሲከፍለው ከሚገባው ካሣ የሚታሰብ ነው።

24.6 ከቀያቸው የተገለሉ የገዳይ ዘመዶች ወደቀያቸው መመለሻ ገደብ

የገዳዩ ሉካዎች ገዳዩን ሰው ወዲያውኑ ቢያቀርቡም የተገደለው ሰው ለቅሶ እስከሚነሳ ድረስ ከገዳዩ ጋር በአያት የሚገናኙ ሉካዎች ከቀያቸው ተገልለው መቆየት አለባቸው። ለቅሶ ከተነሳ በኋላ ሽማግሌ ልከውና ለእምባ ብር 3,000 /ሦስት ሺህ ብር/ በቅድሚያ ከፍለው ወደቀያቸው ይመለሳሉ። ገንዘቡም ወደፊት ከሚከፈለው የደም ካሣ የሚታሰብ ይሆናል። ሉካዎቹ ወደ ቤታቸው ከመመለሳቸው በፊት ገዳዩን የማቅረብ ግዴታ መግባት አለባቸው።

24.7 በመንግሥት ሕግ ተቀጥቶ ከኅብረተሰቡ ጋር መቀላቀያ ሥርዓት

በመንግሥት ሕግ መሠረት ተፈርዶበት ቅጣቱን ጨርሶ ወደቀየው የሚመለስ ሰው በጉራጌ ቺጫ መሠረት ይጠየቃል። ሆኖም መጀመሪያ ተከሳሹ በመንግሥት ሕግ እንጂ በጉራጌ ቺጫ አልዳኘም ያለ ከሆነ ሲመለስ በደረጃው ሙሉ ቺጫ ይጠየቃል፤ ተበዳዩ ወገን በጉራጌ ቺጫ አልዳኝም ብሎ በመንግሥት ሕግ ካስቀጣው ግን የሽማግሌዎች አስተያየት ተጨምሮበት ደሙ በባሕል መሠረት በወግ ይለቅ።





24.8 በፍርድ ወይም በሕመም የሞተ ነፍሰ-ገዳይ ደም አጨራረስ

ነፍሰ-ገዳይ በመንግሥት ፍርድ ወይም በሕመም ቢሞት ደሙ በወግ ይለቅ።

24.9 የተገዳደሉ ሰዎች ደም አጨራረስ

ሁለት ሰዎች ቢገዳደሉ ደማቸው በወግ ይለቅ።

24.10 ከአንድ ሰው በላይ በእጁ ሰው የጠፋበት ወንጀለኛ ቅጣት

አንድ ሰው ከአንድ ሰው በላይ ቢገድል በሞተው በእያንዳንዱ ሰው ብዛት በግድያው ደረጃና ቺጫ መሠረት የደም ካሣ ይከፍላል።

24.11 በጋራ የተፈጸመ ግድያ

ብዙ ሰዎች ሆነው አንድን ሰው በጋራ የገደሉ እንደሆነ እያንዳንዳቸው በተናጠል በደም ተጠያቂ ይሆናሉ። ከሦስቱ የግድያ ደረጃዎች በየትኛው እንደሚጠየቁ ጉዳዩን በሚያዩ ሽማግሌዎች ይወሰናል።

24.12 በእጅዋ ሰው የጠፋባት ሴት ሙሪና ሉካ

አንዲት ሴት ሰው ስትገድል ለወንዱ እንደሚደረገው ሙሪዋ ዘመዶችዋ መሆን አለባቸው። ሉካዎችዋም ይጠየቃሉ።

24.13 ፅንስ የማስወረድ ጥፋት

ሦስት ወር የሞላው ፅንስ ማስወረዱ የተረጋገጠበት ሰው በደም ሤራ መሠረት በደረጃው በገዳይነት ተጠያቂ ይሆናል። የሚከፍለውም ካሣ ለደም ከተመደበው ብር 30,000 /ሠላሣ ሺህ ብር/ ጀምሮ ወደታች እንደ ወንጀሉ አፈጻጸም በሽማግሌዎች ይወሰን።

**24.14 የግድያ ስንዘራ**

ለግድያ ሡንዝሮ ያቆሰለ ሰው በሦስቱ የግድያ እርከኖች መሠረት የቁም ደም ይከፍላል:: ቮጫውም ብር 10, 000 /አሥር ሺህ ብር/ ሆኖ አካል ያጎደለ እንደሆነ በአካል ጉድለት ሤራ መሠረት በተጨማሪ እንዲከፍል ይጠየቃል::

**24.15 ደም ይጀፑርኳ በየ**

አንድ ነፍስ - ገዳይ በጉራጌ ሤራ መሠረት የተወሰነውን ገንዘብ ከፍሎ፣ ተገልሎ መኖርን አሟልቶ እና ሁኔታውን በወግ ጨርሶ ካጠናቀቀ በኋላ ደሙ በዚሁ ያልቅስታል::

**24.16 ሡንዝሮ መሣት**

ተኩሶ፣ ወርውሮ ወይም በስለት ሰውን ለመግደል ሞክሮ የሳተ በሰው ግድያ ሤራ መሠረት ከሦስት ደረጃዎች በአንዱ ይጠየቃል:: ድርጊቱ በግፍ የተፈጸመ ከሆነ ብር 5,000 /አምስት ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል::

**24.17 በፌቅ ሣምቧ/ሳምባ ደም ጃብሮት**

ሌባ በቤቱ ውስጥ ገብቶ ሲሠርቅ ባለቤቱ ወይም በቤቱ ውስጥ ያለ ማንም ሰው ቢገድለው የሟች ሌባ ደም ደመ-ከልብ ሆኖ ደሙን በፍየል ሣምባ ይጨርስ::

**24.18 ሌባ በግድያ ወይም በአካል ማጉደል የሚጠየቅበት ሁኔታ**

ሌባ ሲሰርቅ ሰው ቤት ገብቶ ባለቤቱን ወይም በቤቱ ውስጥ ያለ ማንኛውም ሰው ቢገድል በግፍ ግድያ ሤራ መሠረት ብር 30,000 /ሠላሣ ሺህ ብር/ ካሣ ይከፍላል:: አካል ያጉደለም እንደሆነ በአካል ማጉደል ሤራ መሠረት ይጠየቃል:: እንደሁኔታው በመግደል ሙከራም ሊጠየቅ ይችላል:: የተሠረቀ ንብረት ካለም ለባለቤቱ ይመለሳል፤





የጠፋው ንብረትም የተጠቀመበት ከሆነ ግምቱን ይከፍላል::

**24.19 የገዳይን አዕምሮ ሁኔታ በሃኪም ማረጋገጥ**

አንድ ዕብድ ሰው ቢገድል መጀመሪያ የገዳዩ ሰውዬ አእምሮ በእርግጥ የተቃወሰና ያበደ መሆኑ በታወቀ ሐኪም መረጋገጥ አለበት::

**24.20 የዕብድ ዘመዶች ተጠያቂነትና የእጅ አዙር ግድያ**

የገዳዩ ዘመዶች ዕብድ መሆኑን እያወቁ ተገቢ ጥንቃቄ ሳያደርጉ ቀርተው ዕብዱ ሰውዬ ሌላ ሰው ከገደለ ከዚህ በላይ በ24.19 የተወሰነው እንደተጠበቀ ሆኖ የገዳዩ ዘመዶች ለሟች ቤተሰብ ብር 5,000 /አምስት ሺህ ብር/ የደም ካሣ ይከፍላሉ:: በእጅ አዙር የሌላ ሰው መጠቀሚያ ከሆነ ግን በደም ሤራ መሠረት በደረጃው ይጠየቃል::

**24.21 የእጅ አዙር ግድያ**

አንድ እብድ ሰው በእጅ አዙር ሌላ ሰው እንዲገድል የተደረገ እንደሆነና በእጅ አዙር አስገዳዩ ድርጊትም በመረጃ ተደግፎ ሊታወቅ ከተቻለ በእጅ አዙር አስገዳዩ በደረጃው በደም ተጠያቂ ይሆናል:: ገዳዩ ዕብድ መሆኑ በሐኪም የተረጋገጠው ሰው ወገኖችም የተፈጸመው ግድያ በእጅ አዙር ለመሆኑ የተረጋገጠ ማስረጃ ማቅረብ አለባቸው:: ማስረጃ ከሌለ ግን ከተጠያቂነት አይድኑም::

**24.22 ኸገንደር ንጉሥ/አዝማች ግድያ ካሣ**

አንድ ኸገንደር ንጉሥ /አዝማች ቢገደል ለደም የሚከፈለው ካሣ ከሌላ ሰው ደም ካሣ ጥቂት ልዩነት እንዲኖረው ባህል ስለሆነ በግፍ አገዳደል ደረጃ ሲሆን ብር 1,000 /አንድ ሺህ ብር/ በሰው ደም ካሣ ላይ ተጨምሮ ገዳዩ ይከፍላል:: ግድያው በመዳራና ኸመዳራ

መዳራ ሲሆንም ጭማሪው ካሣ ክፍያው በዚያው ደረጃ ይታሰባል።

24.23 የቆየ ድብደባ ያስከተለው ሞት

አንድ ሰው ቀደም ሲል በሌላ ሰው ተመትቶ ከቆየ በኋላ ቢሞት በደም መጠየቁ ሁኔታ በጥንቃቄ የሚታይ ጉዳይ ነው። በመሠረቱ ሰውየው ታርቆ ተነስቶ ወደ ሥራው ከተመለሰ በኋላ ቢሞት የደም ካሣ መጠየቅ የለበትም። ሆኖም በቂ ምክንያት ኖሮ ከተጉጂ ወገን ጥያቄ ከቀረበ፣

ሀ. በተመታበት ወቅት ሐኪም የአደጋውን ደረጃና አስጊነት ሁኔታ ያረጋገጠበት ማስረጃ መቅረብ አለበት።

ለ. ተደብዳቢው ሰው ሲታረቅ እንደ አደጋው ሁኔታ ስምምነቱን በሽማግሌና በወግ ይጨርስ።

ሐ. በቂ ማስረጃ ያለው ከሆነ ሰው ሞተብኝ ያለው ወገን ከደብዳቢው ሉካ 12 ሙሪ ጠርቶ በደም ሜራ መሠረት ሊታይ ይችላል።

24.24 የግድያ ዛቻ

ለመግደል የዛተና ያስፈራራ ሰው ጉዳዩ በሥርዓት ተጣርቶና ታይቶ እንደ ሁኔታው በሽማግሌ ይለቅ።






# ምዕራፍ አሥራ ሁለት

## በቋንቋ ስለመጠቀም

### አንቀጽ ሃያ አምስት

25.0 ቋንቋ ለአንድ ሕዝብ መግባቢያ፣ የሐሳብ መለዋወጫ፣ የማንነት መገለጫና የባህልም ነፀብራቅ ስለሆነ መገልገያ መሆን እንጂ መጥፋት የለበትም።

25.1 አንድ ቋንቋ ወደ ተከታይ ትውልዶች መተላለፍ የሚችለው እያንዳንዱ ተወላጅ በቋንቋው የመጠቀም ባህል ሲያዳብር ስለሆነ ጉራጌ የሆነ ሁሉ በተቻለው መጠን ቋንቋው እንዳይጠፋ አስተዋጽኦ ያድርግ።

25.2 በጉራጌ የባህል ሸንጎዎች ሁሉ ውይይቶችና ውሳኔዎች በጉራጊኛ ቋንቋ መካሄድ አለባቸው።

25.3 በከተማ የሚኖሩ የጉራጌ ተወላጆች ልጆቻቸው የጉራጊኛ ቋንቋ እንዲያውቁ ጥረት ማድረግ አለባቸው። ይህንን ባያደርጉ በቋንቋው አለመዳበር ወይም መዳከም ባደረጉት አስተዋጽኦ በታሪክ ተጠያቂ ይሆናሉ።

25.4 የጉራጊኛ ቋንቋ ከመድከምና ከመጥፋት ማዳን እንዲቻል ጉራጌ የሆኑ ሰዎች እርስ በርሳቸው ሲነጋገሩ በተቻለ መጠን በቋንቋቸው መጠቀማቸው ወሳኝ ስለሆነ በንቃት እንዲገለገሉበት ተወስኖአል።

25.5 የጉራጊኛ ቋንቋ በትምህርት ቤቶች በትምህርት ፕሮግራም ውስጥ ገብቶ ተማሪዎች እንደ አንድ ትምህርት እንዲማሩትና መጻሕፍትም እንዲዘጋጁ ጥረት ይደረግ።

25.6 ሥነጽሁፎች በጉራጊኛ እንዲዳብሩ ደራሲያንን ማበረታታት ይገባል።

25.7 የጉራጊኛ ቋንቋ ይዳብር ሲባል የሁሉም ጉራጌዎች ቋንቋዎች እንደ ቀበሌኛነታቸው ቢስፋፉ የቀረበ ግንኙነት

ስላላቸው በቀላሉ መግባባት ደረጃ ሊደርሱ ስለሚችሉ በሁሉም አቅጣጫ ጥረት መደረግ አለበት።

25.8 የጉራጊኛ ቋንቋ ደረጃ በደረጃ በሣይንሣዊ መንገድ የማስተማሪያና የሥራ ቋንቋ እንዲሆን መታቀድና ጥረት ማድረግ ይገባል።

25.9 ቤተ-ጉራጌን ሁሉ ለማገናኘት የሚችሉ ቀበልኛዎች በባለሙያዎች እንዲጠኑ በጣም አስፈላጊ በመሆኑ በምሁራን ላይ አደራ ተጥሎአል።






## ምዕራፍ አሥራ ሦስት

## ኧቿጫ ማስፈጸሚያ ተጓዳኝ ሁኔታዎች

የጉራጌ ባህላዊ የአስተዳደርና የፍትሕ ሥርዓቶች ማስፈጸሚያ ዘዴዎች የተለያዩና በርካታም ናቸው። ከብዙ ዘመናት ጀምሮ ሲሠራባቸው ያሉ ባሕላዊ የአስተዳደርና የፍትህ መጠበቂያ ሥርዓቶች ነበሩ፤ አሉም። በሂደት ጠቀሜታቸው የተረጋገጠ ስለሆነ መተግበራቸው መቀጠል አለበት። ለዚህም ኧጕንደር ንጉሥ አንዱ ምሳሌ ነው።

### አንቀጽ ሃያ ስድስት

### 26.1 ኧጕንደር ንጉሥ

26.1.1 በጉራጌ ባህል ኧጕንደር ንጉሥ /አዝማች ተብሎ የሚነግሰው የበኩር ወንድ ልጅ ነው። ይኸውም በደቂቃዎችም ቢሆን ቀድሞ የተወለደው ልጅ ማለት ነው። እርሱ ሰውረር በኸረ/ አካል ጉድለት ወይም ማስተዳደር የማያስችለው ሌላ ችግር ካለ ወንድ ልጅ ካለው የመጀመሪያ ልጁ ይነግሣል። ወንድ ልጅ ከሌለው ግን በዕድሜ ተከታይ ወንድሙ ይነግሣል። ይህንን ሁሉ የሚወስነው ጥሾ ነው።

26.1.2 ከፍ ብሎ በ26.1.1 የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ በአንድ ቤተሰብ ሁለት ሰው ወይም ሁለት ወንድማማቾች በአንድ ጊዜ ማንገሥ ከጉራጌ ሤራ ውጪ ነው። ችግሮች ሲፈጠሩም መፍትሔ መስጠት ያለበት ጥቡ ስለሆነ ሥርዓት እንዳይፋለስ ማድረግ አለበት።

26.1.3 ኧጕንደር ንጉሥ/አዝማች ሆነው ከአካባቢው ተለይተው ከተማ የሚኖሩ አሉ፣ የዕለት ተዕለት ሥራዎች በአካባቢው በሚኖሩ በአቢያዎቻቸው/ በወኪሎቻቸው አማካይነት ይከናወናል። አልፎ አልፎ ግን ቁም ነገሮች በሚወስኑበትና ፈችት

በሚደረግበት ጊዜ አዝማቾቹ በአካል ይገኛሉ:: ስለዚህ ችግር ስለሌለ በዚሁ መሠረት ይቀጥል::

## 26.2 <u>ጉርዳ /ቃል ኪዳን</u>

26.2.1 በጉራጌ ባህል ሲሠራበት የነበረና ያለ ሁለት ወይም ከዚያም በላይ የሆኑ ወገኖች በመካከላቸው መጠቃቃት፣ ጠላትነት፣ አለመተማመን ወዘተ... እንዲጠፋና በመተጋገዝ በመተማመን፣ በመግባባትና ግጭትን በማስወገድ ጉዳያቸው መልካም ፍጻሜ እንዲያገኝ የሚያደርጉበት እርስ በርሳቸው የሚገቡት ቃል - ኪዳን <u>ጉርዳ</u> ስለሆነ በጉራጌ ቊጫ ከፍተኛ ሥፍራ አለው::

26.2.2 ጉርዳ የተያያዙ ወገኖች መሐላ አይማማሉም፤ ምክንያቱም ጉርዳው ከመደበኛው መሐላ የከበደና አሣሪ ባህል በመሆኑ ነው:: ሆኖም ጉርዳ የተያያዙ ሰዎች የተካካዱ እንደሆነ የጉርዳ ዳኛው ሁለቱንም ወገኖች ማስማሚያ መንገድ ካላገኘ ተበደልኩ ባዩ ወገን በዳዩን በቊጫ ዳኛው ፊት በጉርዳ ጊዜ ከማለው በተጨማሪ ሊያስምለው ይችላል::

26.2.3 ጉርዳ በጉራጌ ኅብረተሰብ ውስጥ ብዙ ችግሮችንና አደጋዎችን የቀረፈና የሚቀርፍ ሥርዓት ስለሆነ ሲሠራበት በነበረው አኳኋን ተጠናክሮ እንዲቀጥል ቊጫ ውስጥ ተመልክቶአል::

## 26.3 <u>ኸተራት</u>

26.3.1 ተከራካሪ ወይም ተፋላሚ ወገኖች ኖረው በተፋፋመ ጥል ወይም ትግል ውስጥ ባሉበት ወቅት በጉራጌ ባህል መሠረት ሽማግሌዎች ጥሉን አብርደው በሰከነ ሁኔታ ጉዳዩን ለማየት





እንዲያስችል በሽማግሌዎቹ እስከተወሰነ ጊዜ ድረስ ተፋላሚ ወገኖች ማናቸውም ተፃራሪ የሆነ እርምጃ እንዳይወስዱ የሚያግድ ማህበራዊ ግዴታን የሚያስገባ ሥርዓት ስለሆነና ጠቀሜታውም ከፍተኛ በመሆኑ ቊጫ ውስጥ ገብቶአል::

26.3.2 ኸተራት መከበር አለበት:: ስለዚህ ኸተራት ያፈረሰ ወገን እንደ ጉዳዩ ቀላልነትና ክብደት በባህል ዳኞች/ሽማግሌዎች ተገምግሞ ከብር 100 እስከ ብር 15,000/ከአንድ መቶ እስከ አሥራ አምስት ሺ.ህ ብር/ ቅጣት ይከፍላል::

## 26.4 <u>ፊቸት/ኸትም/ መስዋዕት</u>

26.4.1 በጉራጌ ባህል በቤተ- ዘመድ፣ በጥብ፣ በክፍለ-ሕዝብ ወይም ከዚያም በላይ በሆነ ደረጃ ተሰባስቦ መስዋዕት በማዘጋጀት የሚመራረቅበትና ምልጃ የሚቀርብበት የዘመድ መገናኛና ለባህል ሽግግር ጠቀሜታ ያለው ሥርዓት ስለሆነ ተሻሽሎ ይቀጥል::

26.4.2 ፊቸት በሚደረግበት ጊዜ በአንዳንድ አካባቢ የጥቦች ወይም የጐሣዎች መፎካከሪያና ከማን አንሼ ውድድር በማድረግ የሚታረዱ ከብቶች ብዛት አዲስና ባህሉን የሚበክል ክስተት ስለሆነ ፊቸት የሚያደርጉ ወገኖች ሁሉ ጥንቃቄ እንዲያደርጉ ጥብቅ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል::

## 26.5 <u>ቃማ/ዋስ</u>

26.5.1 በጉራጌ ባህል አንድ ሰው ዋስ እንዲጠራ ሲጠየቅ ዋስ የመጥራት ግዴታ አለበት:: ዋስ የሆነው ሰውም ለተዋሰው ሰውና ጉዳይ ተጠያቂ ነው:: ዋሱ የገባውን ግዴታ መፈጸም አለበት::

በሚደረግበት ጊዜ አዝማቾቹ በአካል ይገኛሉ:: ስለዚህ ችግር ስለሌለ በዚሁ መሠረት ይቀጥል::

## 26.2 ጉርዳ /ቃል ኪዳን

26.2.1 በጉራጌ ባህል ሲሠራበት የነበረና ያለ ሁለት ወይም ከዚያም በላይ የሆኑ ወገኖች በመካከላቸው መጠቃቃት፣ ጠላትነት፣ አለመተማመን ወዘተ... እንዲጠፋና በመተጋገዝ በመተማመን፣ በመግባባትና ግጭትን በማስወገድ ጉዳያቸው መልካም ፍጻሜ እንዲያገኝ የሚያደርጉበት እርስ በርሳቸው የሚገቡት ቃል - ኪዳን ጉርዳ ስለሆነ በጉራጌ ቺጫ ከፍተኛ ሥፍራ አለው::

26.2.2 ጉርዳ የተያያዙ ወገኖች መሐላ አይማማሉም፤ ምክንያቱም ጉርዳው ከመደበኛው መሐላ የከበደና አሣሪ ባህል በመሆኑ ነው:: ሆኖም ጉርዳ የተያያዙ ሰዎች የተካካዱ እንደሆነ የጉርዳ ዳኛው ሁለቱንም ወገኖች ማስማሚያ መንገድ ካላገኘ ተበደልኩ ባዩ ወገን በዳዩን በቺጫ ዳኛው ፊት በጉርዳ ጊዜ ከማለው በተጨማሪ ሊያስምለው ይችላል::

26.2.3 ጉርዳ በጉራጌ ኅብረተሰብ ውስጥ ብዙ ችግሮችንና አደጋዎችን የቀረፈና የሚቀርፍ ሥርዓት ስለሆነ ሲሠራበት በነበረው አኳኋን ተጠናክሮ እንዲቀጥል ቺጫ ውስጥ ተመልክቶአል::

## 26.3 ኸተራት

26.3.1 ተከራካሪ ወይም ተፋላሚ ወገኖች ኖረው በተፋፋመ ጥል ወይም ትግል ውስጥ ባሉበት ወቅት በጉራጌ ባህል መሠረት ሽማግሌዎች ጥሉን አብርደው በሰከነ ሁኔታ ጉዳዩን ለማየት





እንዲያስችል በሽማግሌዎቹ እስከተወሰነ ጊዜ ድረስ ተፋላሚ ወገኖች ማናቸውም ተፃራሪ የሆነ እርምጃ እንዳይወስዱ የሚያግድ ማህበራዊ ግዴታን የሚያስገባ ሥርዓት ስለሆነና ጠቀሜታውም ከፍተኛ በመሆኑ ቺጫ ውስጥ ገብቶአል::

26.3.2 ኸተራት መከበር አለበት:: ስለዚህ ኸተራት ያፈረሰ ወገን እንደ ጉዳዩ ቀላልነትና ክብደት በባህል ዳኞች/ሽማግሌዎች ተገምግሞ ከብር 100 እስከ ብር 15,000/ከአንድ መቶ እስከ አሥራ አምስት ሺህ ብር/ ቅጣት ይከፍላል::

## 26.4 ፊቾት/ኸትም/ መስዋዕት

26.4.1 በጉራጌ ባህል በቤተ- ዘመድ፣ በጥብ፣ በክፍለ-ሕዝብ ወይም ከዚያም በላይ በሆነ ደረጃ ተሰባስቦ መስዋዕት በማዘጋጀት የሚመራረቅበትና ምልጃ የሚቀርብበት የዘመድ መገናኛና ለባህል ሽግግር ጠቀሜታ ያለው ሥርዓት ስለሆነ ተሻሽሎ ይቀጥል::

26.4.2 ፊቾት በሚደረግበት ጊዜ በአንዳንድ አካባቢ የጥቦች ወይም የጐሣዎች መፎካከሪያና ከማን አንሼ ውድድር በማድረግ የሚታረዱ ከብቶች ብዛት አዲስና ባህሉን የሚበክል ክስተት ስለሆነ ፊቾት የሚያደርጉ ወገኖች ሁሉ ጥንቃቄ እንዲያደርጉ ጥብቅ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል::

## 26.5 ቻማ/ዋስ

26.5.1 በጉራጌ ባህል አንድ ሰው ዋስ እንዲጠራ ሲጠየቅ ዋስ የመጥራት ግዴታ አለበት:: ዋስ የሆነው ሰውም ለተዋሰው ሰውና ጉዳይ ተጠያቂ ነው:: ዋሱ የገባውን ግዴታ መፈጸም አለበት::

26.5.2 ዋስ የሆነ ሰው ተፈላጊውን ሰው ባያቀርብ ወይም የገባውን ሌላ ግዴታ ባይፈጽም ወይም ራሱም መቅረብ እምቢ ቢል በቃወ ሥነ-ሥርዓት መሠረት ግዴታውን እንዲወጣ ይጠየቃል:: ተገቢ እርምጃዎች ሁሉ በየደረጃቸው ተወስደው እምቢ ካለ ይረገማል:: ማለት «ተቸግረህ በጉራጌ ፊት ቆመህ አንቅ ለመለመን የሚያደርስ ችግር ይግጠምህ!!» በማለት ሽማግሌዎች እርግማን ይስጡ:: በአጠቃላይ የቃወ ሥነ-ሥርዓትም ይፈጸምበት::

## 26.6 ቃ ወ

26.6.0 አንድ የጉራጌ ተወላጅ የሆነ ሰው በአካባቢ ሽማግሌ ወይም በጥብ ወይም በጉራጌ ስብሰባዎች ለተለያዩ ጉዳዮች አስፈላጊ ሆኖ እንዲቀርብ ወይም እንዲፈጽም ሲጠየቅ ቀርቦ የተጠራበትን ጉዳይ ተረድቶ ሽማግሌ ለሚያቀርብለት ጥያቄ ምላሽ የመስጠት ግዴታ አለበት::

26.6.1 ተፈላጊው የጉራጌ ተወላጅ የሆነው ሰው ወደ ተፈለገበት ጉባዔ እንዲቀርብ መጀመሪያ አንድ ሰው ይላክበታል:: በመጀመሪያ መልክት መሠረት ቀርቦ የተፈለገበትን ጉዳይ ተረድቶ ከሽማግሌዎች ጋር ከተነጋገረ ሽማግሌዎች ጉዳዩን ያያሉ::

26.6.2 በመጀመሪያ . ጥሪ ካልቀረበ ለሁለተኛ ጊዜ ሌላ ሰው ተጨምሮ ጥሪው ይቀርብለታል::

26.6.3 በሁለተኛው ጥሪም ካልቀረበ ለሦስተኛ ጊዜ ሌላ ሰው ተጨምሮ ወደቤቱ በመሄድ እንዲቀርብ ይጠየቃል::





26.6.4 በሦስተኛው ጥሪም ካልቀረበ ወይም ካልፈጸመና ዘመዶቹም ሊያቀርቡት ወይም ሊያስፈጽሙ ካልቻሉ እንደ ጉዳዩ ሁኔታና ደረጃ ቃወ ይገባበታል:: ይኸውም በሜራገኝ ወይም በሙራገኝ: ወይም በጥብ፣ ወይም በክፍለ ሕዝብ ወይም በጉራጌ ሸንጎ በሚወስነው መሠረት ይፈጸማል::

26.6.5 ቃወ የተገባበት ሰው በድርጊቱ ተጸጽቶ ሽማግሌዎችን በትህትና ከቀረበ የሽማግሌዎችን መልዕክት ባለማክበሩ በቤቱ ውስጥ ከብት ታርዶ ይበላና ጉዳዩ ይታያል:: በእምቢተኝነቱ ከቀጠለ ግን ሽማግሌዎች እዚያው እርግማን ያወርዳሉ፣ ጂፓ/ምንጣፍ ሞንጨ፣ ቤደር ነቆሪ፣ እንጣር ሰፖሪ ይወጨይ:: በዚህ አኳኋን ተረግሞ ከኅብረተሰቡ ይወጣል:: ከዚህ በፊት ሲሠራበት በነበረው መሠረት ከሁሉም በኩል ይገለላል::

26.6.6 እምቢተኛ የሆነውና ከኅብረተሰቡ የተገለለው ሰው ተጸጽቶ ይቅርታ ሲጠይቅ፣መጀመሪያ ጥሪ ሲተላለፍለት ባለመቅረቡ ጥሪ ሲተላለፍለት በተጠየቀበት ጉዳይ በየደረጃው ታይቶ ብርቱ ቅጣት ይፈጸምበታል:: በየደረጃው ባሉ የጉራጌ የቼጫ ሽማግሌዎች ጉዳዩ ታይቶ የተሰጠው ቅጣት በሙሉ መፈጸሙን በሽማግሌዎቹ ሲረጋገጥ እርግማኑ ሊነሳለት ይችላል::

## 26.7 ወግ

26.7.1 ወግ የጉራጌ ባህል ሕግ አማካሪ ሲሆን፣ ጉራጌ የሰየመው ቅርኝ/ቅርነ ለመጨረስ እንጂ ለገንዘብ ወይም ለንግድ አይደለም:: ጉራጌ በይፋ አውቆ የሰየመውም አንድ ወግ ብቻ ነው፤ እርሱም ጌታ ክፍለ-ሕዝብ ውስጥ ያለ ነው::

26.7.2 በመሠረቱ ወግ ሽማግሌ ከሚመድብለት የአገልግሎት ዋጋ በላይ ማስከፈል አይችልም፤ ተገቢም አይደለም።

26.7.3 በአሁኑ ጊዜ ያለው ወግ የጥንቱን ሥርዓት አፍርሶ ከፍተኛ ገንዘብ ስለሚያስከፍልና ጉዳይ አጋጥሞአቸው ለማማከር ወደ ወጉ ቤት የሚሄዱ ሰዎች ወጉን ሊያገኙ ባለመቻላቸው መጉላላታቸው በየአቅጣጫው ቀርቦአል።

26.7.4 ወጉ የተሰየመበትን ቅርኝ/ቅርነ የመጨረስ ተግባሩን ብቻ መፈጸም በመሆኑ፣

ሀ. ለአንድ የደም ጉዳይ ከግራ ቀኙ ብር 20 በድምሩ ብር 40 /አርባ/ ብቻ ይከፈለው።

ለ. ለሌሎች ጉዳዮች ከግራ ቀኙ ብር 15 በድምሩ ብር 30 /ሠላሣ/ ብቻ ይከፈለው።

26.7.5 ወጉ ወደ ጉራጌ ሸንጎ ተጠርቶ ከሕዝብ የቀረበበት ሮሮ ይገለጽለት። ጉራጌ በሰየመው መሠረት መሥራት መቻሉን ለሸንጎው ያረጋግጥ። ክፍያውም በቂጫ በተወሰነለት መሠረት ይሁን። የአሁን ድርጊቱን ማረምና ወደተሰየመበት መሠረታዊ ዓላማ የማይመለስ ከሆነ የጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ የሕዝቡን ችግር ለማቃለል የሚያስችለው መንገድ ይፈልጋል።

## 26.8 ጨቀሟ/ጥቆማ

26.8.1 በቂጫ ውስጥ የተደነገጉት ደንቦች በምስጢርም ሆነ በይፋ የጣሰ ተወላጅ ያየ ማናቸውም ሰው በተገቢ መረጃ አስደግፎ ጥቆማ ማቅረብ አለበት።





26.8.2 ጠቋሚው ያቀረበው ጥቆማ ትክክል ሆኖ ከተገኘና የጥቆማ ገንዘብ እንዲከፈለው ከጠየቀ ቂጫ ያፈረሰው ወገን ከሚከፍለው ቅጣት 10% /አሥር በመቶ/ <u>የጨቀሟ</u> ይከፈለዋል። ሆኖም የጥቆማው አመጣጥ በጥንቃቄ ከተገመገመ በኋላ ብቻ ይከፈል።

26.8.3 ጥቆማው ሐሰት ከሆነ በሐሰት ጠቋሚው የተጠቆመበት ሰው ጥፋቱ ተረጋግጦ ሊከፍለው ከነበረው ቅጣት 10% /አሥር በመቶ/ ቅጣት ይክፈል።

## 26.9 መሮ /ጠበቃ

26.9.1 በጉራጌ ባህል መሠረት ጉዳዬን እራሴ ተከራክሬ እወጣዋለሁ ካላለ በስተቀር ማናቸውም ሰው መሮ/ጠበቃ ማቆም መብቱ ነው።

26.9.2 አንድ ሰው በሽምግልና ተሰይሞ ላየው ጉዳይ መሮ መቆም አይችልም።

## 26.10. ሄቶ /ዛር (ምስክር)

26.10.1 በጉራጌ ባህል ሄቶ/ዛር ሁለት ዓይነት አለው። አንደኛው በቀጥታ ስለአየውና ስለሚያውቀው ጉዳይ የሚሰጠው መደበኛ ምስክርነት ነው። ሁለተኛው ግን አንድ ወንጀል ሰርቶአል ተብሎ የተጠረጠረ ሰው ተወላጅ በመሆኑና በተበዳይ ወገን ሙሪ በመጠራቱ ስለድርጊቱ አጣርቶና አረጋግጦ በመሐላ የሚሰጠው ምስክርነት ነው።

26.10.2 ሄቶ/ዛር ሙሪ የለውም። ማለት ዛሩ ቢያጠፋ ከተወላጆቹ መካከል ሙሪ አይጠራም።

26.10.3 ሄቶ/ዛር ለመሆን የሚቀርበው ወይም የሚሰየመው ሰው ለምስክርነት የበቃ፣ ማኅበራዊ

ነውር የሌለበትና ከአእምሮ እውክታ ነፃ የሆነ መሆን አለበት፡፡

26.10.4 አንድ ሰው በፈጸማቸው አስነዋሪ ተግባራት ምክንያት ሕብረተሰቡ ሰውረር/ጉድለት ስላለበት ዛር ኤሰንት ነው ካለው ምስክር ሊሆን አይችልም፡፡

## 26.11 ጥረ አውዶት/ኦዶት

26.11.1 ጥረ አውዶት/ኦደት /የሐሰት ምስክርነት መስጠት በጉራጌ ባህል የተወገዘና ነውር ነው፡፡

26.11.2 የሐሰት ምስክር በሰው ሕይወትና ንብረት ላይ ከፍተኛ አደጋና ጥቃት የሚያደርስና ፍትሕንም የሚያዛባ ስለሆነ በቀጥታ መስካሪም ሆነ በሙሪነት ተጠርቶ በሐሰት መመስከራቸው በማስረጃ ከተረጋገጠ እርግማኑና ዛር ኤስጓትነቱ እንደተጠበቁ ሆነው በገንዘብ ይቀጣሉ፡፡

26.11.3 በሐሰት የመሰከረ ሰው በሐሰት የመሰከረበት ወንጀል ቢወሰን ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሤራ ሂሣብ $1/_3$ /ሲሶውን/ በቅጣት መልክ ይከፍላል፡፡

26.11.4 የሐሰት ምስክሮች መስክረው ሽማግሌዎችም በምስክሮቹ ቃል መሠረት የፍርድ ውሳኔ ሰጥተው በአፈጻጸም ደረጃ ላይ እንዳለ ምስክሮቹ የሐሰት መሆናቸው ከተረጋገጠ የፍርድ ውሳኔው እንደተፈጸመ ተቆጥሮ በአንቀጽ 26.11.3 እንደተመለከተው ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሤራ ሂሣብ $1/_3$ /ሲሶውን በቅጣት መልክ በሐሰት መስካሪው ይከፍላል፡፡

26.11.5 ከሳሽ በሐሰት ማስረጃ መሠረት አስፈርዶ ከረታና አፈጻጸሙም ካለቀ በኋላ በሐሰት መረጃ ተመሥርቶ መወሰኑ በበቂ መረጃ ከተረጋገጠ





በሐሰት የተፈረደበት ወገን ያወጣውን ኪሣራ አለአግባብ ረቺው ተክቶ እንደ ጉዳዩ ሁኔታና ደረጃ ከብር 300-1,000 /ከሦስት መቶ እስከ አንድ ሺ.ህ ብር/ የሞራል ካሣ በሐሰት ለመሰከረበት ሰው ይከፍላል፡፡

## 26.12 ቴ የ /መሐላ

26.12.1 በጉራጌ ዳኛና ከሳሽ በቀጥተኛ መንገድ አይምሉም፡፡ በቀጥታ የሚምለው ምስክር ነው፡፡ ሆኖም ተከሳሽ ዳኞቹን «ዘንጋኛ ናምኹወይ? ቂጥየ ታዘውንዩ ባኹዋ ንግቫ ወይ?» ብሎ ሲጠይቃቸው ዳኞቹ አዎን ካሉትና ከተስማማ ዳኞቹ የመሐላ ቃል እንደሰጡ ይቆጠራል፡፡

26.12.2 እስከ ዛሬ ድረስ ባለው ሁኔታ እንደታየው በጉራጌ ክፍለ-ሕዝቦች በአንዳንዶቹ ለምስክርነት የተጠራ ሰው የምስክርነት ቃሉን ከመስጠቱ በፊት ይምላል፡፡ በሌሎቹ ግን አስቀድሞ መስክሮ ይምላል፡፡ ይህ የተዘበራረቀ አሠራር ታርሞ ሤራው አንድ ወጥ ይሁን፡፡

26.12.3 ከዚ.ህ በላይ በአንቀጽ 26.12.2 በተደነገገው መሠረት በሁሉም ክፍለ-ሕዝቦች አንድ የምስክርነት ቃል የሚሰጥ ሰው ከመመስከሩ በፊት ቃለ መሐላውን መስጠት አለበት፡፡

26.12.4 ለምስክርነት የተጠሩ ሰዎች በትክክል ለመመስከር ቴየ/ቃለ መሐላ ስጡ ሲባሉ እምቢ ካሉ ከሳሽ ሊረታ ይችላል እንጂ እንዲምሉ አይገደዱም፡፡

ነውር የሌለበትና ከአእምሮ እውክታ ነፃ የሆነ መሆን አለበት::

26.10.4 አንድ ሰው በፈጸማቸው አስነዋሪ ተግባራት ምክንያት ሕብረተሰቡ ሰውረር/ጉድለት ስላለበት ዛር ኤሰንት ነው ካለው ምስክር ሊሆን አይችልም::

## 26.11 ጥረ አውዶት/ኦዶት

26.11.1 ጥረ አውዶት/ኦደት /የሐሰት ምስክርነት መስጠት በጉራጌ ባህል የተወገዘና ነውር ነው::

26.11.2 የሐሰት ምስክር በሰው ሕይወትና ንብረት ላይ ከፍተኛ አደጋና ጥቃት የሚያደርስና ፍትሕንም የሚያዛባ ስለሆነ በቀጥታ መስካሪም ሆነ በሙሪነት ተጠርቶ በሐሰት መመስከራቸው በማስረጃ ከተረጋገጠ እርግማኑና ዛር ኤስንትነቱ እንደተጠበቁ ሆነው በገንዘብ ይቀጣሉ::

26.11.3 በሐሰት የመሰከረ ሰው በሐሰት የመሰከረበት ወንጀል ቢወሰን ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሜራ ሂሣብ $1/_3$ /ሲሶውን/ በቅጣት መልክ ይከፍላል::

26.11.4 የሐሰት ምስክሮች መስክረው ሽማግሌዎችም በምስክሮቹ ቃል መሠረት የፍርድ ውሳኔ ሰጥተው በአፈጻጸም ደረጃ ላይ እንዳለ ምስክሮቹ የሐሰት መሆናቸው ከተረጋገጠ የፍርድ ውሳኔው እንደተፈጸመ ተቆጥሮ በአንቀጽ 26.11.3 እንደተመለከተው ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሜራ ሂሣብ $1/_3$ /ሲሶውን በቅጣት መልክ በሐሰት መስካሪው ይከፍላል::

26.11.5 ከሳሽ በሐሰት ማስረጃ መሠረት አስፈርዶ ከረታና አፈጻጸሙም ካለቀ በኋላ በሐሰት መረጃ ተመሥርቶ መወሰኑ በበቂ መረጃ ከተረጋገጠ





በሐሰት የተፈረደበት ወገን ያወጣውን ኪሣራ አለአግባብ ረቺው ተክቶ እንደ ጉዳዩ ሁኔታና ደረጃ ከብር 300-1,000 /ከሦስት መቶ እስከ አንድ ሺህ ብር/ የሞራል ካሣ በሐሰት ለመሰከረበት ሰው ይከፍላል::

## 26.12 ቴ የ /መሐላ

26.12.1 በጉራጌ ዳኛና ከሳሽ በቀጥተኛ መንገድ አይምሉም:: በቀጥታ የሚምለው ምስክር ነው:: ሆኖም ተከሳሽ ዳኞቹን «ዘንጋኛ ናምኹወይ? ቂጥየ ታዘውንዬ ባኹዋ ንግባ ወይ?» ብሎ ሲጠይቃቸው ዳኞቹ አዎን ካሉትና ከተስማማ ዳኞቹ የመሐላ ቃል እንደሰጡ ይቆጠራል::

26.12.2 እስከ ዛሬ ድረስ ባለው ሁኔታ እንደታየው በጉራጌ ክፍለ-ሕዝቦች በአንዳንዶቹ ለምስክርነት የተጠራ ሰው የምስክርነት ቃሉን ከመስጠቱ በፊት ይምላል:: በሌሎቹ ግን አስቀድሞ መስክሮ ይምላል:: ይህ የተዘበራረቀ አሠራር ታርሞ ሜራው አንድ ወጥ ይሁን::

26.12.3 ከዚህ በላይ በአንቀጽ 26.12.2 በተደነገገው መሠረት በሁሉም ክፍለ-ሕዝቦች አንድ የምስክርነት ቃል የሚሰጥ ሰው ከመመስከሩ በፊት ቃለ መሐላውን መስጠት አለበት::

26.12.4 ለምስክርነት የተጠሩ ሰዎች በትክክል ለመመስከር ቱየ/ቃለ መሐላ ስጡ ሲባሉ እምቢ ካሉ ከሳሽ ሊረታ ይችላል እንጂ እንዲምሉ አይገደዱም::

ነውር የሌለበትና ከአእምሮ እውክታ ነፃ የሆነ መሆን አለበት::

26.10.4 አንድ ሰው በፈጸማቸው አስነዋሪ ተግባራት ምክንያት ሕብረተሰቡ ሰውረር/ጉድለት ስላለበት ዛር ኤሰንት ነው ካለው ምስክር ሊሆን አይችልም::

26.11 ጥረ አውዶት/ኦዶት

26.11.1 ጥረ አውዶት/ኦደት /የሐሰት ምስክርነት መስጠት በጉራጌ ባህል የተወገዘና ነውር ነው::

26.11.2 የሐሰት ምስክር በሰው ሕይወትና ንብረት ላይ ከፍተኛ አደጋና ጥቃት የሚያደርስና ፍትሕንም የሚያዛባ ስለሆነ በቀጥታ መስካሪም ሆነ በሙሪነት ተጠርቶ በሐሰት መመስከራቸው በማስረጃ ከተረጋገጠ እርግማትና ዛር ኤሰንትነቱ እንደተጠበቀ ሆነው በገንዘብ ይቀጣሉ::

26.11.3 በሐሰት የመሰከረ ሰው በሐሰት የመሰከረበት ወንጀል ቢወሰን ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሜራ ሂሣብ 1/3 /ሲሶውን/ በቅጣት መልክ ይከፍላል::

26.11.4 የሐሰት ምስክሮች መስክረው ሽማግሌዎችም በምስክሮቹ ቃል መሠረት የፍርድ ውሳኔ ሰጥተው በአፈጻጸም ደረጃ ላይ እንዳለ ምስክሮቹ የሐሰት መሆናቸው ከተረጋገጠ የፍርድ ውሳኔው እንደተፈጸመ ተቆጥሮ በአንቀጽ 26.11.3 እንደተመለከተው ተወንጃዩ ሊከፍለው ከነበረው ሜራ ሂሣብ 1/3 /ሲሶውን በቅጣት መልክ በሐሰት መስካሪው ይከፍላል::

26.11.5 ከሳሽ በሐሰት ማስረጃ መሠረት አስፈርዶ ከረታና አፈጻጸሙም ካለቀ በኋላ በሐሰት መረጃ ተመሥርቶ መወሰኑ በበቂ መረጃ ከተረጋገጠ





በሐሰት የተፈረደበት ወገን ያወጣውን ኪሣራ አለአግባብ ረቺው ተክቶ እንደ ጉዳዩ ሁኔታና ደረጃ ከብር 300-1,000 /ከሦስት መቶ እስከ አንድ ሺህ ብር/ የሞራል ካሣ በሐሰት ለመሰከረበት ሰው ይከፍላል::

26.12 ቴ የ /መሐላ

26.12.1 በጉራጌ ዳኛና ከሳሽ በቀጥተኛ መንገድ አይምሉም:: በቀጥታ የሚምለው ምስክር ነው:: ሆኖም ተከሳሽ ዳኞቹን «ዘንጋኛ ናምኹወይ? ቂጥየ ታዘውንዬ ባኹዋ ንግኻ ወይ?» ብሎ ሲጠይቃቸው ዳኞቹ አዎን ካሉትና ከተስማማ ዳኞቹ የመሐላ ቃል እንደሰጡ ይቆጠራል::

26.12.2 እስከ ዛሬ ድረስ ባለው ሁኔታ እንደታየው በጉራጌ ክፍለ-ሕዝቦች በአንዳንዶቹ ለምስክርነት የተጠራ ሰው የምስክርነት ቃሉን ከመስጠቱ በፊት ይምላል:: በሌሎቹ ግን አስቀድሞ መስክሮ ይምላል:: ይህ የተዘበራረቀ አሠራር ታርሞ ሜራው አንድ ወጥ ይሁን::

26.12.3 ከዚህ በላይ በአንቀጽ 26.12.2 በተደነገገው መሠረት በሁሉም ክፍለ-ሕዝቦች አንድ የምስክርነት ቃል የሚሰጥ ሰው ከመመስከሩ በፊት ቃለ መሐላውን መስጠት አለበት::

26.12.4 ለምስክርነት የተጠሩ ሰዎች በትክክል ለመመስከር ቴየ/ቃለ መሐላ ስጡ ሲባሉ እምቢ ካሉ ከሳሽ ሊረታ ይችላል እንጂ እንዲምሉ አይገደዱም::

## ምዕራፍ አሥራ አራት

## ያፈጻጸም ተዋረድ፣ ያስፈጻሚ ምርጫ፣ስብሰባዎች

### አንቀጽ ሃያ ሰባት

27. **እቺጫ አፈጻጸም ሥርዓት ተዋረድ**

27.1 እጉራጌ ቂጫ በተግባር ሲተረጎም እንደየጉዳዩ ባሕርይ እንደሚከተለው እንዲፈጸም ተወስኖአል::

27.1.1 በሜራ ዳኘ /ዳነ

27.1.2 በሙራ ገኘ/ገነ

27.1.3 በጥብ

27.1.4 በክፍለ-ሕዝብ

27.1.5 በጉራጌ ሸንጎ

27.2 ቂጫውን በማስፈጸም ረገድ ችግሮች ቢኖሩ በዚሁ በጉራጌ ቂጫ መሠረት መፍትሔ እንዲያገኙ በየደረጃው ጥረት መደረግ አለበት::

### አንቀጽ ሃያ ስምንት

28. **እቺጫ አስፈጻሚ ምርጫ**

28.1 እጉራጌ ቂጫ ትክክለኛ አፈጻጸም እንዲኖረው አስተማማኝ የሆኑ ሽማግሌዎችን መርጦ የሚመድበው በየደረጃው ያለው የጉራጌ ሕዝብ ነው:: ከጉራጌ ክልል ውጪ የሚኖሩ ተወላጆችንም በሚመለከት አፈጻጸሙ በዚሁ መንገድ ይሆናል::





28.2 የተመረጡ ዳኞችም/ሽማግሌዎችም ይህንን ቂጫ ሲያስፈጽሙ ከዚህ በፊት በነበረው መሠረት ቃለ መሐላ መፈጸም አለባቸው:: ሁሉም ነገር በዚያው በመሐላው መሠረት ይፈጸም:: የእያንዳንዱ ክፍለ-ሕዝብ ሸንጎም በደረጃው በባህል ደንብ መሠረት ቂጫውን ይፈጽም፣ ያስፈጽም::

### አንቀጽ ሃያ ዘጠኝ

29. **የጉራጌ የባህል ዳኞች**

29.1 በየክፍለ-ሕዝቡ በየጊዜው የሚመረጡ ወይም በቋሚነት የተመደቡ የባህል ዳኞች አሉ:: እነዚህም እቺጫ ዳኘ/ዳነ፣ የኾርር ዳኘ/ዳነ፣ ያንቂት ዳኘ/ዳነ፣ እጉርዳ ዳኘ/ዳነ የሚባሉትን ያጠቃልላል::

29.2 ከእነዚህ ሁሉ <u>እጉርዳ ዳኘ/ዳነ</u> የተለየ ነው:: ይኸውም <u>ጉርዳ</u> /ቃል ኪዳን የተግባቡ ሁለት ወገኖች ተስማምተው ጉዳያቸውን እንዲያይላቸውና በዚያ ጉዳይ ላይ ብቻ ፍርዱን እንዲሰጥ የሚመርጡት ቋሚ ያልሆነ ዳኛ ነው::

29.3 ሌሎች የጉራጌ የባህል ዳኞች ማለት እሜራ ዳኘ/ዳነ፣ እገኘ ዳኘ/ዳነ፣ እጥብ ዳኘ/ዳነ፣ የክፍለ ሕዝብ ዳኘ/ዳነ፣ የጉራጌ ሸንጎ ዳኘ/ዳነ ተብለው የተሰየሙ ወይም ለተወሰነ ጊዜ በተሰብሳቢዎቹ ተመርጠው የሚመደቡ የቂጫ ዳኞች አሉ::

29.4 በየክፍለ-ሕዝቡ አጠቃላይ የቂጫ ዳኘ/ዳነ መኖርን በሚመለከት ከኄታ በስተቀር በሌሎቹ አንድ ብቻ የሆነ አጠቃላይ የቂጫ ዳኘ/ዳነ የላቸውም:: በአብዛኞቹ ዋና ዋና ጥቦችን የሚወክሉና እኩል ደረጃ ያላቸው እስከ አራት አጠቃላይ የቂጫ ዳኞች አሉ:: ለምሳሌ በቸሀ፣ በእገር፣ በእኖር፣ በእንደገኝ ያሉትን መጥቀስ ይቻላል:: አሠራሩ በዚሁ መሠረት መቀጠል ይቻላል::

## ምዕራፍ አሥራ አራት

## ያፈጻጸም ተዋረድ፣ ያስፈጻሚ ምርጫ፣ስብሰባዎች

### አንቀጽ ሃያ ሰባት

27. ### ኽቑጫ አፈጻጸም ሥርዓት ተዋረድ

27.1 ኽጉራጌ ቑጫ በተግባር ሲተረጎም እንደየጉዳዩ ባሕርይ እንደሚከተለው እንዲፈጸም ተወስኖአል::

27.1.1 በሜራ ዳኘ /ዳነ

27.1.2 በሙራ ገኘ/ገነ

27.1.3 በጥቭ

27.1.4 በክፍለ-ሕዝብ

27.1.5 በጉራጌ ሸንጎ

27.2 ቑጫውን በማስፈጸም ረገድ ችግሮች ቢኖሩ በዚሁ በጉራጌ ቑጫ መሠረት መፍትሔ እንዲያገኙ በየደረጃው ጥረት መደረግ አለበት::

### አንቀጽ ሃያ ስምንት

28. ### ኽቑጫ አስፈጻሚ ምርጫ

28.1 ኽጉራጌ ቑጫ ትክክለኛ አፈጻጸም እንዲኖረው አስተማማኝ የሆኑ ሽማግሌዎችን መርጦ የሚመድበው በየደረጃው ያለው የጉራጌ ሕዝብ ነው:: ከጉራጌ ክልል ውጪ የሚኖሩ ተወላጆችንም በሚመለከት አፈጻጸሙ በዚሁ መንገድ ይሆናል::





28.2 የተመረጡ ዳኞችም/ሽማግሌዎችም ይህንን ቑጫ ሲያስፈጽሙ ከዚህ በፊት በነበረው መሠረት ቃለ መሐላ መፈጸም አለባቸው:: ሁሉም ነገር በዚያው በመሐላው መሠረት ይፈጸም:: የእያንዳንዱ ክፍለ-ሕዝብ ሸንጎም በደረጃው በባህል ደንብ መሠረት ቑጫውን ይፈጽም፣ ያስፈጽም::

### አንቀጽ ሃያ ዘጠኝ

29. ### የጉራጌ የባህል ዳኞች

29.1 በየክፍለ-ሕዝቡ በየጊዜው የሚመረጡ ወይም በቋሚነት የተመደቡ የባህል ዳኞች አሉ :: እነዚህም ኽቑጫ ዳኘ/ዳነ፣ የኻርር ዳኘ/ዳነ፣ ያንቂት ዳኘ/ዳነ፣ ኽጉርዳ ዳኘ/ዳነ የሚባሉትን ያጠቃልላል::

29.2 ከእነዚህ ሁሉ <u>ኽጉርዳ ዳኘ/ዳነ</u> የተለየ ነው:: ይኸውም <u>ጉርዳ</u> /ቃል ኪዳን የተግባቡ ሁለት ወገኖች ተስማምተው ጉዳያቸውን እንዲያይላቸውና በዚያ ጉዳይ ላይ ብቻ ፍርዱን እንዲሰጥ የሚመርጡት ቋሚ ያልሆነ ዳኛ ነው::

29.3 ሌሎች የጉራጌ የባህል ዳኞች ማለት ኽሜራ ዳኘ/ዳነ፣ ኽገኘ ዳኘ/ዳነ፣ ኽጥቭ ዳኘ/ዳነ፣ የክፍለ ሕዝብ ዳኘ/ዳነ፣ የጉራጌ ሸንጎ ዳኘ/ዳነ ተብለው የተሰየሙ ወይም ለተወሰነ ጊዜ በተሰብሳቢዎቹ ተመርጠው የሚመደቡ የቑጫ ዳኞች አሉ::

29.4 በየክፍለ-ሕዝቡ አጠቃላይ የቑጫ ዳኘ/ዳነ መኖርን በሚመለከት ከቺታ በስተቀር በሌሎቹ አንድ ብቻ የሆነ አጠቃላይ የቑጫ ዳኘ/ዳነ የላቸውም:: በአብዛኞቹ ዋና ዋና ጥቦችን የሚወክሉና እኩል ደረጃ ያላቸው እስከ አራት አጠቃላይ የቑጫ ዳኞች አሉ:: ለምሳሌ በቸሀ፣ በኧገር፣ በእኖር፣ በእንደገኝ ያሉትን መጥቀስ ይቻላል:: አሠራሩ በዚሁ መሠረት መቀጠል ይቻላል::

## አንቀጽ ሠላሣ

## 30. የየክፍለ-ሕዝቡ ባሕላዊ ሽንጎ መሰብሰቢያ ሥፍራዎች

30.1 በአሁኑ ጊዜ የየክፍለ-ሕዝቡ ሸንጎ መሰብሰቢያ ቦታዎች ስሞች የሚከተሉት ናቸው።

| ተ.ቁ. | የክፍለ-ሕዝብ/ኅብረተሰብ ስም | የሸንጎው መሰብሰቢያ ቦታ ስም |
|---|---|---|
| 00 | 01 | 02 |
| ሀ. | ቸሃ | የጆካ |
| ለ. | ጉሜሬ | » |
| ሐ. | ጌታ | ቋንጤ |
| መ. | ኧዣ | ጹሰነ |
| ሠ. | ሞኽርና አክሊል | እምር የጠቆርፓ/የዝራ |
| ረ. | እኖርና ኤነር | ወሸ |
| ሰ. | እንደጎኝ | ሻርካ |
| ሸ. | መቆርቆር | የገዛ |
| ቀ. | የአበሽጌ ጉራጌዎች | ውርእሃ/የጆሐር ዋርኬ |





### 30.2 አጠቃላይ ሸንጎ መሰብሰቢያ ሥፍራና ሰብሳቢ

#### 30.2.1 መሰብሰቢያ ሥፍራ

የሰባት ቤት ጉራጌ አጠቃላይ ባህላዊ ሸንጎ መሰብሰቢያ ቦታን በተመለከተ ቀድሞ ሞጬ፣ ቀጥሎ የጆካ፣ ከዚያም እምድብር እንደነበረ ተገልጾአል:: አሁንም የሚካሄደው በእምድብር መሆኑ ታውቆአል:: የወደፊቱ አጠቃላይ መሰብሰቢያ ቦታን በተመለከተ ሕዝቡ እየተመካከረ በማዟዟር በእያንዳንዱ ክፍለ-ሕዝብ ባህላዊ ሸንጎ መሰብሰቢያ ሥፍራ ሊያደርገው ይችላል::

#### 30.2.2 ሰብሳቢ

የሰባት ቤት ጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ ቋሚ ሆኖ የተመደበ ሰብሳቢ የለውም:: በስብሰባው ወቅት ሽማግሌዎቹ ለሰብሳቢነት ብቃት አለው የሚሉትን ሰው ከመካከላቸው የዕለቱ ወይም ጉዳዩ እስከሚጠናቀቅ ድረስ በሰብሳቢነት መርጠው ይሰይሙታል:: ዛሬም የሚሠራው በዚሁ መሠረት ስለሆነ ይኸው አሠራር ይቀጥል::

### 30.3 የአጠቃላይ ሸንጎ መሰብሰቢያ ወቅት

30.3.1 የሰባት ቤት ጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ እስከ ዛሬ ድረስ የተወሰነ መሰብሰቢያ ጊዜ የለውም:: በሰባት ቤት ጉራጌ ባህላዊ ሸንጎ ደረጃ መታየት ያለባቸው ጉዳዮች በክፍለ-ሕዝቦች በኩል ሲከሰቱና ቺጫን የሚመለከቱ ጉዳዮች ሲኖሩ ሽማግሌዎች በመላላክ ተጠራርተው ይሰበሰባሉ:: ወደፊት ግን የሸንጎው መሰብሰቢያ ጊዜ የተመደበ እንዲሆን ተወስኖአል:: ስለዚህ ባህላዊ ሸንጎ በሚከተለው ሁኔታ ይሰበሰባል::

30.3.2 አሁን ብዙ የተደነገጉ ሜራዎች ስላሉ ለመተግበር፣ አፈጻጸሙን ለመከታተልና አስፈላጊ ማሻሻያዎችና እርማቶች ቢኖሩ ለማስተካከል በየሦስት ወር ይሰብሰብ::

30.3.3 አጣዳፊ የሆኑ ሜራዎች ተግባራዊነት ፈር መያዝ መጀመሩ ሲረጋገጥ ሸንጎው በስድስት ወር አንድ ጊዜ ይሰብሰብ፣

30.3.4 የሜራዎቹ አፈጻጸም እስከነ ደረጀ ሲደርስ ሸንጎው በዓመት አንድ ጊዜ ይሰብሰብ:: ሆኖም አስቸኳይ ጉዳዮች ካጋጠሙም ልዩ ጥሪ በማድረግ መሰብሰብ ይቻላል::

## አንቀጽ ሠላሣ አንድ

## የስብሰባ ሥነ-ሥርዓትና ውጤት ምዝገባ

### 31.1 ሰዓት ማክበር

የዓለማችን ሥልጣኔ ከደረሰበት አኳያ ጊዜ ፍጹም ወርቅ ስለሆነ ሁሉም ሰዓት አክብሮ መገኘት ወሳኝ ነውና ጊዜን እንድንሠራበት እንጂ እንዳይሠራብን ብርቱ አደራ ተጥሎአል::

### 31.2 በጊዜ በወጉ መጠቀም

ውሳኔ ላይ ከመድረስ በፊት የመረጃዎች በአግባብ መቅረብና መብላላት፣ የሃሳብ ሙሉ በሙሉ መንሸራሸር በጣም ተገቢ ነው፤ የማያስፈልጉ ድግግሞሾችን በማስቀረትና ጊዜ በመቆጠብ ከመሰላቸት የፀዳና ውል ያለው ውሳኔ ማስገኘቱ የጋራ ኃላፊነት በመሆኑ ሁሉም ሁኔታዎችን እንዲያከብር ይገባል::

### 31.3 ባርኔጣና ስብሰባ

የሚካሄዱ ስብሰባዎችና ጉባዔዎች እንደሁኔታው ዳኝነት የሚታይባቸው ፣ ፍትሕ የሚጠበቅባቸውና ውሳኔ





የሚተላለፍባቸው መድረኮች በመሆናቸው ከበሬታ ሊላበሱ ይገባል:: በመሆኑም በማናቸውም ስብሰባዎችና ጉባዔዎች በሃይማኖት ምክንያት ራስ ላይ ከሚደረጉ ቆቦች፣ ኮፍያዎችና ጥምጥሞች እንዲሁም ከጤና ጋር በተያያዘ በሃኪም ከሚታዘዙ መጠቀሚያዎች ውጪ/በስተቀር ባርኔጣ፣ መለዮ ወይም ማናቸውም ዓይነት የራስ መጠለያ ማድረግ ፍጹም የተከለከለ ነው::

### 31.4 የስብሰባዎች ውጤት በሰነድነት ምዝገባ

የሚደረጉ ውይይቶችና ትንታኔዎች በተለይም የሚተላለፉ ውሣኔዎች ለታሪክ መዘክርነትና ለአርአያነት ብሎም ቼጫውን ለማዳበርና ለማሻሻል ከፍተኛ ጠቀሜታ ስለሚኖራቸው በቋሚ መዝገብ እየተመዘገቡና በትክክል ለመሥፈራቸው ቢያንስ በዳኛና በፀሐፊ ፊርማ እየተረጋገጡ በሰነድነት መያዛቸው ሊታለፍ የማይገባው ኃላፊነት ነው::



30.3.2 አሁን ብዙ የተደነገጉ ሜራዎች ስላሉ ለመተግበር፣ አፈጻጸሙን ለመከታተልና አስፈላጊ ማሻሻያዎችና እርማቶች ቢኖሩ ለማስተካከል በየሦስት ወር ይሰብሰብ::

30.3.3 አጣዳፊ የሆኑ ሜራዎች ተግባራዊነት ፈር መያዝ መጀመሩ ሲረጋገጥ ሸንጎው በስድስት ወር አንድ ጊዜ ይሰብሰብ፣

30.3.4 የሜራዎቹ አፈጻጸም እስከነ ደረጃ ሲደርስ ሸንጎው በዓመት አንድ ጊዜ ይሰብሰብ:: ሆኖም አስቸኳይ ጉዳዮች ካጋጠሙም ልዩ ጥሪ በማድረግ መሰብሰብ ይቻላል::

## አንቀጽ ሠላሣ አንድ

## የስብሰባ ሥነ-ሥርዓትና ውጤት ምዝገባ

### 31.1 ሰዓት ማክበር

የዓለማችን ሥልጣኔ ከደረሰበት አኳያ ጊዜ ፍጹም ወርቅ ስለሆነ ሁሉም ሰዓት አክብሮ መገኘት ወሳኝ ነውና ጊዜን እንድንሠራበት እንጂ እንዳይሠራብን ብርቱ አደራ ተጥሉአል::

### 31.2 በጊዜ በወጉ መጠቀም

ውሳኔ ላይ ከመድረስ በፊት የመረጃዎች በአግባብ መቅረብና መብላላት፣ የሃሳብ ሙሉ በሙሉ መንሸራሸር በጣም ተገቢ ነው፤ የማያስፈልጉ ድግግሞሾችን በማስቀረትና ጊዜ በመቆጠብ ከመሰላቸት የፀዳና ውል ያለው ውሳኔ ማስገኘቱ የጋራ ኃላፊነት በመሆኑ ሁሉም ሁኔታዎችን እንዲያከብር ይገባል::

### 31.3 ባርኔጣና ስብሰባ

የሚካሄዱ ስብሰባዎችና ጉባዔዎች እንደሁኔታው ዳኝነት የሚታይባቸው ፣ ፍትሕ የሚጠበቅባቸውና ውሳኔ





የሚተላለፍባቸው መድረኮች በመሆናቸው ከበሬታ ሊላበሱ ይገባል:: በመሆኑም በማናቸውም ስብሰባዎችና ጉባዔዎች በሃይማኖት ምክንያት ራስ ላይ ከሚደረጉ ቆቦች፣ ኮፍያዎችና ጥምጥሞች እንዲሁም ከጤና ጋር በተያያዘ በሃኪም ከሚታዘዙ መጠቀሚያዎች ውጪ/በስተቀር ባርኔጣ፣ መለዮ ወይም ማናቸውም ዓይነት የራስ መጠለያ ማድረግ ፍጹም የተከለከለ ነው::

### 31.4 የስብሰባዎች ውጤት በሰነድነት ምዝገባ

የሚደረጉ ውይይቶችና ትንታኔዎች በተለይም የሚተላለፉ ውሣኔዎች ለታሪክ መዘክርነትና ለአርአያነት ብሎም ቺጫውን ለማዳበርና ለማሻሻል ከፍተኛ ጠቀሜታ ስለሚኖራቸው በቋሚ መዝገብ እየተመዘገቡና በትክክል ለመሥፈራቸው ቢያንስ በዳኛና በፀሐፊ ፊርማ እየተረጋገጡ በሰነድነት መያዛቸው ሊታለፍ የማይገባው ኃላፊነት ነው::



ምዕራፍ አሥራ አምስት

## ልዩ ልዩ ድንጋጌዎች

ከምዕራፍ አንድ እስከ አሥራ አራት በተጠቀሱት ሜራዎች ያልተጠቃለሉ አንዳንድ ሁኔታዎች እዚህ ተመልክተዋል::

### አንቀጽ ሠላሣ ሁለት

32. ከራሱ ክፍለ-ሕዝብ ውጪ በሌላ ክፍለ-ሕዝብ ክልል ወንጀል ፈጻሚ መዳኛ

የአንድ ክፍለ-ሕዝብ ተወላጅ የሆነ ሰው ከራሱ ክልል ውጪ በሌላው ክፍለ-ሕዝብ ውስጥ ወንጀል ሠርቶ ቢገኝ ጥቃት የደረሰበት ክፍል በቀጥታ ሉካዎቹን መጠየቅ ይችላል:: ምክንያቱም አንድ ሰው በየትኛውም የጉራጌ ክፍለ-ሕዝብ ውስጥ ለሠራው ወንጀል በጉራጌ ሜራ መሠረት ሉካዎቹ ተጠያቂ በመሆናቸው ነው::

### አንቀጽ ሠላሣ ሦስት

33. ኅብረተሰቡን የሚያገለግሉ ባህላዊ ድርጅቶች

33.1 በጉራጌ ባህል መሠረት ከጥንት ተያይዘው የመጡ በዕምነቱ መሠረት ለኅብረተሰቡ አገልግሎት ሰጥተው የገንዘብ ወይም የዓይነት ስጦታ ወይም ክፍያ የሚደረግላቸው ባህላዊ የእምነት ድርጅቶች መኖራቸው የታወቀ ነው:::

33.2 ኅብረተሰቡ በእምነቱ መሠረት የሚሰጣቸው ባህላዊ አክብሮትና ሥርዓቶችን የመፈጸም ጉዳይ እያንዳንዱ የባህል ድርጅት ሥርዓቱን ጠብቆና ከወቅቱ ጋር አስተካክሎ ሊቀጥል ይችላል:: ሆኖም ኅብረተሰቡ በእምነቱ መሠረት ከባህላዊ ድርጅቶች የሚያገኛቸው አገልግሎቶች ከፍተኛ ወጪን የሚያስከትሉበት እንዳይሆን እንዲያደርጉ ጥብቅ ማሳሰቢያ ተሰጥቶአል::





33.3 ባህል በሃይማኖትና በእምነት፣ ሃይማኖት በእምነትና በባህል ውስጥ ጣልቃ ገብቶ ችግር እንዳይኖር ጥንቃቄ ይደረግ ተብሎ በቂጫ የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ አንዳንዳቹ ባህሎች ጊዜው ሊያከስማቸው የሚችሉ ቢኖሩም ሁሉም በታሪክ ተፈላጊነታቸው የታወቀ ስለሆነ ዝርዝር ታሪካቸው ተመዝግቦ ይቀመጥ::

### አንቀጽ ሠላሣ አራት

34. አጥም ስፓራ/ዘርን የሚነካ ከባድ ስድብ

34.1 መመዘኛዎች እንደጊዜው ይለያዩ እንጂ አጥም ስፓራ ጉራጌ በቂጫ ውስጥ መድቦት ሲሠራበት ያለ ሥርዓት ስለሆነ መመዘኛዎቹ ከጊዜው ጋር ተስተካክለው ይቀጥል::

34.2 ማንኛውም የጉራጌ ተወላጅ የሆነ ሰው ራሱንና ቤተ-ዘመድን የሚያዋርድ፣ ጋብቻ የሚያስከለክል ወዘተ... ያልሆነና ያልተደረገ መጥፎ ነገር በመጥራት ለምሳሌ አዛይ/አዜ (አራንሺ)፣ ዘረቢስ በማለት የተሳደበ ዝርዝር ሁኔታው ተጣርቶ ሲረጋገጥ እስከ ዛሬም ቅጣት እንዳለው የታወቀ ስለሆነ ሥርዓቱ በቂጫው ታቅፎ ይቀጥል::

34.3 በጉራጌ ባህል መሠረት አጥም ስፓራ መሆኑ በመረጃና በሽማግሌዎች ከተረጋገጠ በኋላ እንደ ስድቡ ዓይነትና ደረጃ በሽማግሌዎች ተገምግሞ ከብር 50 እስከ ብር 500 /ከብር ሃምሣ እስከ አምስት መቶ ብር/ ቅጣት ይከፍላል::

## አንቀጽ ሠላሣ አምስት

### 35. ወካሽ ሥቅሮት

በደል ወይም ችግር የደረሰበት ሰው ፍትሕ ሲያጣ ወይም በዳዩን ማወቅ ሳይችል ሲቀር አጥቂውን ለመበቀል ወካሽ መስቀል የተባለ አሠራር መኖሩ ታውቆአል:: ይህ ከሰው ግድያ ጋር ሜራ ውስጥ ተደንግጎ ሊገባ የሚችል ጉዳይ አይደለም:: በዳዩ የሚታወቅ ሰው ከሆነ ፍትሕ እንዳይጓደል የአካባቢ ሽማግሌዎች አውቀውት በሚፈቅዱት መሠረት ሊፈጸም የሚገባው ነው:: ይህንን ሁሉ አሟልቶ ፍትሕ ካጣና ይረዳኛል ብሎ ካመነበት ወካሽ መስቀል አይከለከልም::

## አንቀጽ ሠላሣ ስድስት

### 36. አደጋ አድራሽ እንስሳት

36.1 ተናካሽ ውሻ፣ ተዋጊና ተራጋጭ ከብት ያለው ሰው አደጋ እንዳያደርሱ ብርቱ ጥንቃቄ ማድረግ አለበት::

36.2 ባለንብረቱ ተገቢ ጥንቃቄ ሳያደርግ ቀርቶ ውሻው ወይም ከብቱ በሰው ላይ አደጋ ቢያደርስ የጉዳዩ ሁኔታ ተጣርቶ ከደረሰው ጉዳት ጋር ተመጣጣኝ የሆነ ቅጣት/ካሣ በከብቱ ባለቤት ላይ ሽማግሌዎች ይወስኑ:: አስፈላጊ የሆነ የሕክምና ወጪም ባለንብረቱ ይከፈል::

## አንቀጽ ሠላሣ ሰባት

### 37. የቤተ-ጉራጌ የወደፊት አዝማሚያ

መላ ቤተ-ጉራጌን ባካተተ መልኩ የክልሉን ሁለንተና ለማጥናት እንዲያስችል በ1983 ዓ.ም. በመላ ቤተ-ጉራጌ ተሳትፎ የተዘጋጀው ፊር-ቀዳጅ የጥናት መመሪያ «የጉራጌ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ አጥኚና አማካሪ ግብረ-ኃይል፣ ጉመሥድ 004/83» የተሰኘው ሰነድ ባመላከተው መሠረት በወል ጥረት





የጋራው ዓላማ ግቡን እንዲመታ የሕዝባችን ያላሰለሰ ተሳትፎና ክትትል እንዳይለየው በታሪክ ሰሪው ሕዝብ ስም ማሳሰቢያ ቀርቦአል::

## አንቀጽ ሠላሣ ስምንት

### 38. ከቄጫ መጣስ የሚገኝ ገቢ አጠቃቀም

38.1 የጉራጌን ቄጫ ከጣሱ ተወላጆች የሚሰበሰበው የቅጣት ገንዘብ ለአካባቢው ልማት ሥራ ላይ ይዋል::

38.2 የቄጫ መጣስ ቅጣት ገቢም አሰባሰብና አወጣጥ በሰባት ቤት ጉራጌ ደረጃ በጉሁራልድ ደንብ መሠረት በየቀበሌው በደረጃ የተቋቋመውን መዋቅር በመከተል ተተግብሮ ለዚያው ቀበሌ ልማት ሥራ ይዋል::

38.3 ከገቢው ላይ የጠቋሚ ወጪ የሚከፈለበት መሆኑ ከተረጋገጠ ሂሣቡ ከዚሁ ገቢ ላይ ተቀንሶ ይከፈልና ቀሪው በውሳኔው መሠረት ለቀበሌው ልማት ሥራ ላይ ይዋል::



# ምዕራፍ አሥራ ስድስት

<u>ድምዳሜ</u>

## አንቀጽ ሠላሣ ዘጠኝ

39. <u>የቭጫው ተፈጻሚነት ወሰን</u>

39.1 የጉራጌ ቐጫ በየትም ቦታ የሚኖሩ ተወላጆች ይዳኙበታል፤ ይተዳደሩበታል::

39.2 የጉራጌ ሕዝብ አንድነቱንና ህብረቱን ለመጠበቅ በባህሉ ከወረሳቸው መልካም ቅርሶች አንዱ ይኸው ቐጫ ስለሆነ በባህሉ መሠረት የተደነገጉ ሤራዎች የጉራጌ ተወላጅ የሆነ ሰው ሁሉ የመኖሪያ አካባቢውና የኑሮው ሁኔታ ሳይወስነው የሚተዳደርበትና የሚዳኝበት ሥርዓት ነው::

## አንቀጽ አርባ

40. <u>ቐጫውን አለማክበር የሚያስከትለው እርምጃ</u>

40.0 ጉራጌ የደነገጋቸው ሤራዎችን ለማስፈጸም ከ1-5 ደረጃ ያለው የማስፈጸሚያ ሥርዓት የተዘረጋ መሆኑ በአንቀጽ 27 ስለተገለጸ ቐጫውን አላከብርም፤ አልቀበልም የሚል ሰው ሲያጋጥም በየደረጃው ተመክሮና ተለምኖ ካልተመለሰ፣ የሚከተሉት እርምጃዎች ይወሰዱበታል::

40.1 ከጉራጌ ዕድር ውጪ ይሆናል::

40.2 ከጠቅላላው የጉራጌ ሕብረተሰብ ማኅበር ውጪ ስለሆነ ዋስ አይኖረውም::

40.3 ከእርሱ ጋር እህልና ውሃ አይቀመስም::

40.4 ከጉራጌ ኅብረተሰብ እንዲገለል ይደረጋል::

40.5 እርሱን የሚደግፍ ቢኖር ግብረ አበር ሆኖ እርሱም ከኅብረተሰቡ ይገለላል::





## አንቀጽ አርባ አንድ

41. <u>የቐጫው ሕትመትና ሥርጭት</u>

የጉራጌ ባህል ሤራዎች በጣም ሰፊና ጥልቀት ያላቸው በመሆናቸው ወደፊት እየታየ ተጠንተው መሟላትና የሁሉን ቤተ-ጉራጌ ባህሎች ባካተተ መልኩ እንዲቀናጁ መደረግ አለባቸው:: አሁን እዚህ ቐጫ ውስጥ የተካተቱት ከጊዜው እንቅስቃሴዎች ጋር የተያያዙ በመሆናቸው ቅድሚያ የተሰጣቸው ብቻ ናቸው:: ስለዚህ እነዚህ በጣም ተፈላጊ የሆኑት ሤራዎች ሕዝቡ አውቆአቸው በተግባር እንዲያውላቸው በሰነድነት ታትሞ በሽያጭ እንዲሠራጭ ተወስኖአል::

## አንቀጽ አርባ ሁለት

42. <u>ቐጫውን ስለማሻሻል</u>

ይህ ቐጫ በሙሉም ሆነ በከፊል የሚሻሻሉ ወይም ሌሎች የሚጨመሩ ጉዳዮች ሲኖሩ ከየክፍለ-ሕዝቡ በእኩል ቁጥር በሚወከል የጉራጌ ባሕላዊ ጠቅላላ ሸንጎ ይሻሻላሉ ወይም ይጨመራሉ::

## አንቀጽ አርባ ሦስት

43. <u>ቐጫው የሚፀናበት ጊዜ</u>

ይህ የጉራጌ ቐጫ በአዲስነት የተጨመሩና ነባሮቹም የተሻሻሉበት ሁኔታ ቢኖርም፣ በሰነድነት ተጽፎ ባይታወቅም በዘልማድ ሕዝቡ ሲሠራበት የኖረ ሥርዓት ነው:: አሁን በጠቅላላ ባህላዊ ሸንጎ በተቋቋመው አጥኚ ኰሚቴ ተጠንተውና በጠቅላላ ባህላዊ ሸንጎ ጉባዔ ፀድቀው በሰነድ የሠፈሩ ሤራዎች ጠቅላላ ባህላዊ ሸንጎ መርምሮ ካፀደቀበት ከጥቅምት 20 ቀን 1987 ዓ.ም. ጀምሮ የፀኑ ናቸው::

## ዕዝል I

# ዕዝሎች

### የአጥኚ ኮሚቴ አባላት

### ሀ. ከአገር ቤት

**ሀ.1 ከጌታ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አዝማች ወልዴ ሳፎ
Δ የዛራዳም ቱጎ ዘንጋጋ

**ሀ.2 ከጉሚሬ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ ዳሞ ደሲል ግዛው
Δ ይማም ሰብር ጐታረ

**ሀ.3 ከእኖርና ኤነር ክፍለ-ሕዝብ**

Δ መምሬ ሙሴ ግምበር
Δ አቶ ዜማ ወንቢረ

**ሀ.4 ከቸሃ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ የዋይ ደማም ዘርፉ እንሣ
Δ አቶ ተሰማ አመርጋ

**ሀ.5 ከኧዣ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አቶ ኃይሉ ሀብተማርያም
Δ አዝማች ካሣ ጂዛ

**ሀ.6 ከሞኽርና አክሊል ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አቶ አርጋው ድረታ
Δ አቶ ብሩ ማሬሮ

**ሀ.7 ከመቆርቆር ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አቶ ታደሰ ኃይሌ





**ሀ.8 ከእንደጋኝ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አቶ አድማሴ ወርቂ
Δ አዝማች ካሣ ወልዴ/ወይም አቶ አረጋ ኤርሴዶ ቢመረጡም ተሳትፎአቸው በጣም ውስን ነበር።

**ሀ.9 ከአበሽጌ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አበጋዝ ይርጋ ዘፕሬ
Δ አቶ ፋንቱ ወልደኪዳን

### ለ. ከአዲስ አበባ

**ለ.1 ከጉሕራልድ ዋና መሥሪያ ቤት**

Δ አዝማች ይርጋ ገብሬ ድረታ
Δ አቶ ወልደ ማርያም ወ/ሚካኤል
Δ » ክብረት ኃይሉ
Δ » ደንድር ደንሣሞ

**ለ.2 ከጌታ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ አዝማች ኃይሌ ገብረየሱስ
Δ አቶ ይርጋዓለም ወሰኔ
Δ » ገብሩ አርጋው

**ለ.3 ከቸሃ ክፍለ-ሕዝብ**

Δ ባላምባራስ ብሩ ኖሣሽ
Δ አቶ ሩፋኤል አረጋ
Δ » ገብረዮሐንስ ሞራጋ

ለ.4 ከእኖርና ኤነር ክፍለ-ሕዝብ

- Δ አቶ ኪሩቤል በቃና
- Δ » ዓለማየሁ ነሪ
- Δ አዝማች ወልደጻድቅ ጌብቻረ

ለ.5 ከጉማረ ክፍለ-ሕዝብ

- Δ አቶ አረጋ ሀብተ ወልድ
- Δ ሃጂ መሀዲ ሺህባቦ
- Δ አቶ ወርቁ ንዳ

ለ.6 ከእዣ ክፍለ-ሕዝብ

- Δ አቶ ግዛው ብዛኒ
- Δ » ይጨነቁ ጉዳና
- Δ » በረዳ ኪዳኔ

ሀ.7 ከሙኽርና አክሊል ክፍለ-ሕዝብ

- Δ አቶ ወልዴ ደምሴ
- Δ » ሹምጌታ ገ/ሥላሴ
- Δ » ጌታሁን ቦጋለ

ለ.8 ከእንደገኝ ክፍለ-ሕዝብ

- Δ ዶ/ር ኃይሌ ወልደሚካኤል
- Δ ኢንጂንየር ሀብቴ ወልደዮሐንስ
- Δ አቶ ለማ ደሳለኝ
- Δ » ወልደሰንበት ላጊሶ

አዲስ አበባ ነዋሪ የሰባት ቤት ጉራጌ ተወላጆች በቋጫ አጥኚ ኮሚቴና በልዩ ልዩ የሙያ ግብረ-ኃይሎች ውስጥ ተመርጠው ከተሳተፉት ሌላ ከየክፍለ-ሕዝቡ ብዙ ተወላጆች በጥናቱ ውይይት ተሳትፈው አስተዋጽኦ አድርገዋል።





ሐ. በራስ አነሳሽነት የተሳተፉ

ሐ.1 ከአገር ቤት

በጥናቱ ያገር ቤትን ሕዝብ እንዲወክሉ ከተመረጡት ሌላ ከየክፍለ–ሕዝቡ በፈቃደኝነት ተገኝተው ያዳመጡና አስተያየታቸውን በጥናቱ ኮሚቴ ስብሰባዎች በመገኘት የሰጡ ተወላጅ ፖማግሌዎችና አዛውንቶች ብዛት ከፍተኛ ቢሆንም በተለይ የቅርብ ክትትልና ተሳትፎ ካደረጉት መካከል Δ ዳሞ ኃይሉ ቡሊ፣ Δ አገዛማች ግርር ኵርበጌ፣ Δ አቶ ሀብቴ መራጨ፣ Δ አቶ ግርማ ቃሩ፣ Δ አቶ ኵርጋዘ አሰፋው፣ Δ ኀይታኩየ ሙሉ ደበላ፣ Δ አቶ አሰፋ ቦንገር፣ Δ አዝማች በርታ ወልደጻድቅ በምሳሌነት ተጠቅሰዋል።

ሐ.2 ከአዲስ አበባ

ከአዲስ አበባ ነዋሪ ከሆኑ የጉራጌ ተወላጆች በቋጫ አጥኚ ኮሚቴና በልዩ ልዩ የሙያ ግብረ-ኃይሎች ውስጥ ተመርጠው ከተሳተፉት ሌላ ከየክፍለ-ሕዝቡ ብዙ ሰዎች በጥናት ውይይቶች ተካፍለው ከፍተኛ አስተዋጽኦ አድርገዋል።





## በቋሚው ረቂቅ ሰነድ ላይ ሙያዊ አስተያየት የሰጡ ሙያተኞች

(ሙያተኞቹ አስተያየት የሰጡት በአራት ዋና ዋና የሥራ ዘርፎች በመደራጀት ነበር።)

### ሀ. ከሕግ አኳያ

| | | |
|---|---|---|
| Δ | ፕሮፌሰር ያዕቆብ ኃይለማርያም | ሰብሳቢ. |
| Δ | አቶ ሣህሌ ሀብቴ | ፀሐፊ |
| Δ | ዶ/ር ሸዋረጋ አሥራት | አባል |
| Δ | አቶ ደርባቸው መሐመድ | » |
| Δ | » ማርቆስ ወልደሰንበት | » |
| Δ | » ግርማ ቦጋለ | » |
| Δ | » ወልደሰንበት ገብታ | » |
| Δ | » ገብረየስ ወልደሚካኤል | » |
| Δ | » ንዳው በቃሩ | » |
| Δ | » ሰማ ደሳለኝ | » |
| Δ | ሐጅ አበሻ ያሲኖ | » |

### ለ. ከማህበራዊ አገልግሎት አቅጣጫ

(ትምህርት፣ ጤና፣ ባህል፣ ቋንቋ፣ አካል ማሠልጠኛ ስፖርት)

| | | |
|---|---|---|
| Δ | አቶ ኃይሌ ሸመር | ሰብሳቢ. |
| Δ | » እንዳለ ሸዋንግዛው | ፀሐፊ |
| Δ | አዝማች ይርጋ ገብሬ ድሬታ | አባል |
| Δ | ዶ/ር ይልማ በርታ | » |
| Δ | አቶ አህመዲን ሀሰን | » |
| Δ | » አበራ ወልደጻዲቅ | » |
| Δ | » ወልደብርሃን ሰርሂ | » |
| Δ | » ተስፋዬ ኃይሌ | » |





| | | |
|---|---|---|
| Δ | » አበበ በሻር | » |
| Δ | » ገብረዮሐንስ ሞራጋ | » |
| Δ | ወ/ሮ ዓለምነሽ ኃይለማርያም | » |
| Δ | አቶ አብዱ አማን | » |

### ሐ. ከኤኮኖሚ ልማትና ከኤኮኖሚ አገልግሎት ዘርፍ አኳያ

(ልማት፣ ንግድ፣ መድንና ፋይናንስ ወዘተ.)

| | | |
|---|---|---|
| Δ | አቶ ፍቅሬ ቡታ | ሰብሳቢ. |
| Δ | » ወልደማርያም ወልደሚካኤል | ፀሐፊ |
| Δ | » ይርጋዓለም ወሰኔ | አባል |
| Δ | » ወልደማርያም ገብረሰንበት | » |
| Δ | አቶ ሩፋኤል አረጋ | » |
| Δ | » ሹምጌታ ገብረሥላሴ | » |
| Δ | » ገብሩ አርጋው | » |
| Δ | » ተማም መሐመድ | » |
| Δ | » ቱርጋ ቡታ | » |
| Δ | » ሀብቴ ገብረየሱስ | » |
| Δ | » አድብብ ኬሬ | » |
| Δ | » ወልደጊዮርጊስ ኃይሌ | » |
| Δ | ኢንጂነር ጌታቸው ወልደየስ | » |
| Δ | አቶ ይጨነቁ ጉዳና | » |

### መ. ከአስተዳደርና ከማኔጅመንት አንፃር

| | | |
|---|---|---|
| Δ | አቶ ሣህለማርያም ገብረጊዮርጊስ | ሰብሳቢ. |
| Δ | » ሣህለሥላሴ ብርሃነማርያም | ፀሐፊ |
| Δ | » ኪሩቤል በቀና | አባል |
| Δ | » ዓለማየሁ ነሪ | » |
| Δ | » በላቸው በንቲ | » |
| Δ | » ኃይለመስቀል ኬርጋ | » |
| Δ | » ወርቁ ሰማ | » |

ዕዝል III

የጉራጌ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ አጥኚና
አማካሪ ግብረ- ኃይል
ድርጅታዊ አቋም በ1983 የተነደፈ




* ሳሎታ፣ መልጋ ጣንቁ፣ አዘርዝት በርበሬ፣ ሥልጤ፣ ሌቃ ወላና ወራ ጎንቶር

ማብራሪያ

ሀ/ ማኅበሩን በተመለከተ
ሀ.1/ 1,2+3 በሊቀመንበር ይስተባበራሉ
ሀ.2/ 4,5+6ን በተቀሚ ም/ሊቀመንበር ይስተባበራሉ
ሀ.3/ 7,8+9 በ2ኛ ም/ሊቀመንበር ይስተባበራሉ
ሀ.4/ 10,11+12 በዋና ፀሐፊ ይስተባበራሉ
ሀ.5/ [illegible]

ለ/ ክፍሎችን በተመለከተ
ለ.1/ እያንዳንዱ ክፍል የራሱ ሰብሳቢ፣ ም/ሰብሳቢና ፀሐፊ ይኖረዋል።
ለ.2/ በውስጡም እንደ አስፈላጊነቱ የሚቋቋሙ ንዑሳን ሥራ ተከታታዮች ይኖሩታል።
ለ.2.1/ የክፍሉ የታሪክ ጥናት ተከታታይ
ለ.2.2/ የክፍሉ የፈለም ሥራ ጉዳይ ተከታታይ
ለ.2.3/ " የባሕል ጥናት ተከታታይ
ለ.2.4/ የዕድገት እንቅስቃሴዎችና የወደፊት አቅጣጫ ጥናት ተከታታይ
ለ.2.5/ የክፍሉ የተፈደናገሰ ጉዳይ ተከታታይ
ለ.2.6 የክፍሉ የባህል ጥናት ተከታታይ ማኅበራዊ ቱፊቶች፣ የልማዳዊ ሕክምና የአክል ማሠልጠኛና ስፖርት፣ የተክኖሎጂ ባህል፣ የባሕላዊ አስተዳደርና ፍትሕአዊ ሕጎች ጥናትን ወዘተ.ጨምሮ ይከታተላል።



# ዕዝል IV

## የጉራጊኛ ፊደል ገበታ (የጉራጊኛ አነባበብ መፍቻ)

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1. | ለ | ሉ | ሊ | ላ | ሌ | ል | ሎ |
| 2. | መ | ሙ | ሚ | ማ | ሜ | ም | ሞ |
| 3. | ᎀ | | ᎁ | ሟ | ᎂ | ᎃ | |
| 4. | ረ | ሩ | ሪ | ራ | ሬ | ር | ሮ |
| 5. | ሰ | ሱ | ሲ | ሳ | ሴ | ስ | ሶ |
| 6. | ሸ | ሹ | ሺ | ሻ | ሼ | ሽ | ሾ |
| 7. | ቀ | ቁ | ቂ | ቃ | ቄ | ቅ | ቆ |
| 8. | ቐ | ቑ | ቒ | ቓ | ቔ | ቕ | ቖ |
| 9. | ቈ | | ቊ | ቋ | ቌ | ቍ | |
| 10. | በ | ቡ | ቢ | ባ | ቤ | ብ | ቦ |
| 11. | ᎄ | | ᎅ | ቧ | ᎆ | ᎇ | |
| 12. | ተ | ቱ | ቲ | ታ | ቴ | ት | ቶ |
| 13. | ቸ | ቹ | ቺ | ቻ | ቼ | ች | ቾ |

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 14. | ነ | ኑ | ኒ | ና | ኔ | ን | ኖ |
| 15. | ኘ | ኙ | ኚ | ኛ | ኜ | ኝ | ኞ |
| 16. | ኀ | ኁ | ኂ | ኃ | ኄ | ኅ | ኆ |
| 17. | ⷐ | ⷑ | ⷒ | ⷓ | ⷔ | ⷕ | ⷖ |
| 18. | ኈ | | ኊ | ኋ | ኌ | ኍ | |
| 19. | አ | ኡ | ኢ | ኣ | ኤ | እ | ኦ |
| 20. | ከ | ኩ | ኪ | ካ | ኬ | ክ | ኮ |
| 21. | ኸ | ኹ | ኺ | ኻ | ኼ | ኽ | ኾ |
| 22. | ኰ | | ኲ | ኳ | ኴ | ኵ | |
| 23. | ወ | ዉ | ዊ | ዋ | ዌ | ው | ዎ |
| 24. | ዘ | ዙ | ዚ | ዛ | ዜ | ዝ | ዞ |
| 25. | ዠ | ዡ | ዢ | ዣ | ዤ | ዥ | ዦ |
| 26. | የ | ዩ | ዪ | ያ | ዬ | ይ | ዮ |
| 27. | ደ | ዱ | ዲ | ዳ | ዴ | ድ | ዶ |





| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 28. | ጀ | ጁ | ጂ | ጃ | ጄ | ጅ | ጆ |
| 29. | ገ | ጉ | ጊ | ጋ | ጌ | ግ | ጎ |
| 30. | ጘ | ጙ | ጚ | ጛ | ጜ | ጝ | ጞ |
| 31. | ጐ | | ጒ | ጓ | ጔ | ጕ | |
| 32. | ጠ | ጡ | ጢ | ጣ | ጤ | ጥ | ጦ |
| 33. | ጨ | ጩ | ጪ | ጫ | ጬ | ጭ | ጮ |
| 34. | ፈ | ፉ | ፊ | ፋ | ፌ | ፍ | ፎ |
| 35. | ᎈ | | ᎉ | ፏ | ᎊ | ᎋ | |
| 36. | ፐ | ፑ | ፒ | ፓ | ፔ | ፕ | ፖ |
| 37. | ᎌ | | ᎍ | ፗ | ᎎ | ᎏ | |

# ከአማርኛ ለየት ያለ አነባበብ ያላቸው ሆሄያት በጉራግኛ ቃላት ሲገቡ

3. ᎀ - ᎁ - ሟ - ᎂ - ᎃ
ᎀነ - ኣᎁን - ሟር - ᎂና - እᎃር

8. ቐ - ቑ - ቒ - ቓ - ቔ - ቕ - ቖ
ቐሳ - ቑም - ፉቒ - ቓጣም - ያቔ - ቕጬ - ያንቖ

9. ቌ - ቍ - ቋ - ቌ - ቍ
ቌረ - ትቍ - ቋንጤ - ትቌ - ቍያ

11. ᎄ - ᎅ - ቧ - ᎆ - ᎇ
ᎄራ - ቧሪም - ᎆናት - ᎇራ

15. ኘ ኙ ኚ ኛ ኜ ኝ ኞ
ይህ ሆሄ በጌቲና÷ በእኖሪና÷ በኤነሪና÷
በእንደገኚና አለ::

በቾጊና÷በእኾርና÷በጐማሪና÷የለም::

17. ⶨ ⶩ ⶪ ⶫ ⶬ ⶭ ⶮ
ⶨመሪም-ብⶩት-ትⶪ -ኣⶫ -ትⶬ -ⶭን-ኣⶮ





18. ኈ - ኍ - ኊ - ኌ - ኍ
ኈኈብ - ናኍም - አኊ - ኌት - ኍት

19. አረ አርቾ ኣታርዌ ?

21. ኸኸረም-አኸኺ - ወኻ -ፍኼ - ይሰᎀኽ

22. ኰ - ኲ - ኳ - ኴ - ኵ
ኰር - ዳኲት - ኣኳ - አባኴ - ኵረ

30. ጘ - ጙ - ጚ - ጛ - ጜ - ጝ - ጟ
ጘጘር - ዘንጚ -ዳንጛ- ዳንጜ - ድርጝ - ዳንጟ

31. ጐ - ጒ - ጓ - ጔ - ጕ
ጐበት - ድርጕ - ጓማ - ኣጔ - ጕር

35. ፎ - ᎈ - ፏ - ᎉ - ᎊ - ᎊ
ፎር - ኣᎈ - ፏር - ᎉያት - ᎊረ - ᎊር

37. ፖ - ፑ - ፐ - ፔ - ፑ
ነፖሪም - ንፑር - ይኈርፔ - ዘፑን

## የጉራጌ የሣምንት ቀኖች አጠራር/መጠሪያ

| ተራ ቁጥር | ክፍለ-ሕዝብ | ሰኞ | ማክሰኞ | ረቡዕ | ሐሙስ | አርብ | ቅዳሜ | እሁድ |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 00 | 01 | 02 | 03 | 04 | 05 | 06 | 07 | 08 |
| 1. | ጌታ | ውጠት | መገርገሸያ | ኧሮ | ከምስ | ጅማት | ቀጣትሰንበት | ውርሰንበት |
| 2. | እገር | ውጠት | ውጠትመረጋ | ኧሮ | አሙስ | አዳረ/ጅማት | ቀጣትሰንበት | ውርሰንበት |
| 3. | ቸሃ | ውጠት | ውጠትመረጋ | ኧሮ | አሙስ | አዳረ/ጅማት | ቀጣትሰንበት | ውርሰንበት |
| 4. | ጉሜረ | ውጠት | ውጠትመረጋ | ኧሮ | አሙስ | አዳረ/ጅማት | ቀጣትሰንበት | ውርሰንበት |
| 5. | እኖርና ኤነር | ውጠት | መገርገሸያ | ኧሮ | ከምስ | ጅማት | ቀጣትሰንበት | ውርሰንበት |
| 6. | እንደገኝ | ውጠት | መገርገሸያ | አርቤ | ከምስ | ጅማት | ኤነርገሸያ/ቅዳሜ | አበ |
| 7. | ሞኽርና አክሊል | ውጠት | ውጠትመናግ | ረው | አሙስ | አዳረ | ቀደንሰንበት | ውርሰንበት |





## ጉራጌ ዘመን/ዓመት/ወር አቆጣጠር

| ተራ ቁጥር | በ6 ክፍላተ-ሕዝብ* | በአማርኛ | በሞኽርና አክሊል |
|---|---|---|---|
| 00 | 01 | 02 | 03 |
| 1. | ይዳር | መስከረም | መስከረም |
| 2. | መሸ | ጥቅምት | ጥቅምት |
| 3. | ጥርር/እንተጉጉት | ህዳር | ህዳር |
| 4. | መንገስ | ታኅሣሥ | መንገስ |
| 5. | ወቶ | ጥር | የቡደርዘር |
| 6. | ማዚያ | የካቲት | የራዝዙር |
| 7. | ግርወት | መጋቢት | ይጭወር |
| 8. | ሰርየ | ሚያዝያ | ማዚያ |
| 9. | አምሬ | ግንቦት | ግልዋት |
| 10. | ናሴ | ሰኔ | ሶንየ |
| 11. | ቋቁሜ | ጳጉሜ | ጳጉሜ |
| 12. | መስኽሮ | ሐምሌ | ኣምሌ |
| 13. | ጥርቅምት | ነሐሴ | ነሐሴ |

---

ጌታ ጉሜረ
እገር እንደገኝ
ቸሃ እኖርና ኤነር

# የቃላትና የሐረጐች ትርጉም/ፍቺ/ማብራሪያ

## በጉራጌ ቂጫ ውስጥ የተካተቱ አንዳንድ ቃላትና <u>ሐረጐች ትርጉም/መግለጫ/ማብራሪያ/ፍቺ</u>

1. <u>ቂጫ፣</u>

ሕገ-ቤተጉራጌ፣ (የጉራጌ ባህላዊ ሕግ፣ ያስተዳደርና የፍትሕ ሥርዓት)

2. <u>ኧ፣</u>

በአንዳንድ የጉራጌ ቋንቋ (ለምሳሌ በቼቲና፣ በእኖሪና፣ በኤነሪና እና በእንደገኚና የአማርኛውን «የ» ሆሄ ሊወክል/ሊተካ የሚችል የጉራጊኛ ሆሄ ነው:: ለምሳሌ ኧጉራጌ ቂጫ ሲል የጉራጌ ቂጫ ማለት ነው:: በአነባበብ ወቅት ከአማርኛው «የ» ሆሄ ጋር እየተመሳሰለ እንዳያስቸግር በቂጫው ውስጥ ቃሉ ጉራጊኛ በሚሆንበት ጊዜ በ«የ» ፈንታ ለግልጸት ሲባል «ኧ» ግልጋሎት ላይ እንዲውል ተደርጐአል::

3. <u>ሙራ ደም፣</u>

በግፍና በጭካኔ የሚፈጸም/የሚወሰድ ድርጊት፣ እርምጃ ግድያ ሲሆን፣ ከፍተኛውን ቅጣት ወይም ሙሉ የደም ዋጋ/ካሣ (ጉማ) የሚያስከፍል እርምጃ ማለት ነው::

4. <u>መዳራ፣</u>

በስህተት/በዝንጋታ የሚፈጸም ድርጊት ወይም ግድያ

5. <u>ኸመዳራ መዳራ፣</u>

ፍጹም ባለማወቅ የሚፈጸም ድርጊት/ግድያ፣ «<u>የስህተት ሥህተት</u>»/ «የዝንጋታ ዝንጋታ» ድርጊት ሊባል ይችላል::





6. <u>ሉካ፣</u>

የቅርብ የዝምድና ሐረግ ሲሆን፣ በተፈጸመ ድርጊት፣ግድያ አድራጊ ወይም ገዳይ የካደ እንደሆነ ኃላፊነት እንዲወስድ የሚቆጠር የትውልድ/የዝምድና ሐረግ ነው::

7. <u>ሙሪ፣</u>

ከተቆጠሩት ሉካዎች መሃል የቅርብ ኃላፊነቱን የሚወስዱ/የሚከታተሉ በተጐጂ/በተበዳይ ወገን የሚሰየሙ ተጠሪዎች::

8. <u>ወካሸ ስቅሮት፣</u>

ተበዳይ በዳዩን ማወቅ/ማግኘት ሲሳነው ወይም ፍትሕ ሲጓደልበት በዳዩን ለመበቀል የሚወስደው እርምጃ «<u>ወካሸ ስቅሮት</u>» በመባል ይታወቃል፤ ድርጊቱ በዘልማድ በበዳዩ ላይ ዕክል/ችግር ይፈጥራል የሚል እምነት በአንዳንድ ሰዎች ዘንድ አለ::

9. <u>ኸጐንደር ንጉሥ/አዝማች</u>

ባህላዊ መሪ፣ አስተዳዳሪና ዳኛ ማለት ነው:: ቀደም ሲል እያንዳንዱ ጐሣ ራሱን በራሱ ያስተዳድር በነበረበት ወቅት አንዳንዱ ጐሣ «<u>ኸጐንደር ንጉሥ</u>» የሚባል ባህላዊ መሪ፣ አስተዳዳሪና ዳኛ ነበረው:: መሪውም ከትውልድ ወደ ትውልድ የሚተላለፍ የኃላፊነቱ መለያ የሆነ ጐንደር/አምባር እጁ ላይ ይደረግለታል/ያደርጋል:: ንጉሥ በመሆኑም «<u>ኸጐንደር ንጉሥ</u>» በሚል ስያሜ ሲጠራ/ሲታወቅ ኖሮአል:: ዛሬ ሐረጉ «<u>አዝማች</u>» በሚል ቃል ተተክቶ ባህላዊ መሪዎቹ በዚህ የማዕረግ ስም ይጠራሉ/ይታወቃሉ:: ዛሬም ቢሆን ኃላፊዎቹ ባህላዊ አመራር፣ አስተዳደር፣ ዳኝነት፣ ሽምገላና አስታራቂነት ወዘተ. አገልግሎት ይሰጣሉ:: በገጠሩ መሪዎቹ ሙሉ ጊዜያቸውን ለሕዝብ አገልግሎት ሲያውሉ ሕዝቡ የሙያ፣ የጉልበትና ወዘተ. አገልግሎት ያበረክትላቸዋል::

10. አጥ፟ም ስፓራ፣

ሥነ-ልቦና ሰላቢ/ሰባሪ፣ ጋብቻ ከልካይ፣ ከኅብረተሰብ አግላይ ወዘተ. ከባድ ስድብ «አጥ፟ም ስፓራ» «አጥንት ሰበራ» ይባላል።

11. ቾግ፣

ፍጥምጥም፣ የጋብቻ ቃልኪዳን መግቢያና መተጫጫ ሥርዓት

12. ኧገኒየ፣

የተጫጩ ሴትና ወንድ ከመጋባታቸው በፊት በየፊናቸው በእህት፣ በወንድም፣ በአክስት፣ በአጐትና በዘመድ አዝማድ ቤት እየተዘዋወሩ የሚደረግላቸው መስተንግዶና ግብዣ፣ ሂደቱም የተጋቢዎቹን አካል ያጠነክራል።

13. አዥመኘ/ነ (አግኖት)፣

ሠርግ፣ የሙሽራው አጃቢዎች

14. መሣይት/መሤት፣

በሠርጉ ቀን የሙሽሪት አጃቢ ሴቶች

15. ይፍት ኧዥነር/እዥነር

ከሠርግ በኋላ ወላጆችና ዘመዶች ሙሽሮቹን ከነሚዜዎቻቸው መልስ የሚጠሩበት ባህል

16. ይፍት ዝፓረ፣

ሙሽሪት ከሦስት ወር የጫጉላ ቤት ቆይታ በኋላ ለተወሰነ ጊዜ ወላጆችዋ ዘንድ ተመልሳ የምትቆይበት ወቅት

17. ቢተር ውጦት፣

ትዳር ይዞ ጉጆ መውጣት





18. ኸንቆሮፏት/ያንቆሮፏት፣

ቾግ/የመተጫጨት ቃልኪዳን በመጣሱ/በመፍረሱ ምክንያት ለተጣሰበት ወገን የሚከፈል የሞራል ካሣ

19. ዝማጀ፣

ጠለፋ (የልጃገረድ)

20. አንቂት፣

በባልና ሚስት መሃል የነበረ የጋብቻ ውል የሁለቱ ተጋቢዎች ፈቃደኝነት ተጨምሮበት ውሉ በፍቺ ሲፈርስ «አንቂት ጀፓሪ» ይባላል። ሁለቱም ሕጋዊ ኃላፊነታቸውን አወረዱ/ ተወጡ ማለት ስለሆነ በየፍላጐታቸው ሌላ ጋብቻ ለመፈጸም ሁኔታው ነፃ ያደርጋቸዋል። በባህሉ አንቂት ሴትዋን እንጂ ወንዱን ሌላ ጋብቻ ከመፈጸም አያግደውም፤ በመሆኑም ባህሉ በሚፈቅደው መሠረት ሥርዓቱ ተፈጽሞ ባል ለሚስቱ «ሥርጥ ኸክርኽ» ብሎ ያሰናብታታል፤ ይህም ሌላ ትዳር ለመመሥረት ባለመብት ያደርጋታል።

21. ወግየት፣

ድረፈት/አግብታ የፈታች ሴት፣ ሌላ ባል ስታገባ በጊዜያዊነት መጠሪያዋ

22. ጀፎረ፣

የቀዬ/የገጥ ነዋሪዎች የጋራ መጠቀሚያ፣ መተላለፊያ፣ መግቢያና መውጫ ስፈ መሰብሰቢያ፣ ጠዋት ከብቶች ከመሠማራታቸው በፊት ማታ ደግሞ በየቤታቸው ከመግባታቸው በፊት ማቆሚያ የጋራ ሥፍራ/ጉዳና/መናኸሪያ

23. ሞጣ/ዋድ/ወገር-ዴማ፣

ከፍተኛ መተላለፊያ፣ ከአንድ ክፍለ-ሐዝብ ወደ ሌላ ክፍለ-ሕዝብ የሚያሸጋግር ሰፊና አቋራጭ ጉዳና/መንገድ ተለይቶ በጉሣው ባለቤትነት የሚታወቅ

24. ቓማ፣
ዋስ

25. ቿወ፣

ለኅብረተሰቡ ሥርዓት አልገዛ፣አልዳኝ፣ አልታዘዝ ያለወገን በሸንጉ የተውጣጡና የተመረጡ ሽማግሌች ተሰብስበው እቤቱ በመሄድ የሚወስዱት/የሚፈጽሙት ባህላዊ እርምጃ

26. ወግ፣

«ባህላዊ የፍርድ አማካሪ»፣ በባህል መሠረት የተሰጡ ውሳኔዎች በማንኛውም ወገን ቂም በቀል በማያተርፍ/በማያቆይ መልኩ እንዲያልቁ እንደ ጉራጌ ባህላዊ ሕግ አማካሪ ሊቆጠር በሚችል ወግ በመባል በሚታወቅ ሥርዓት ድምዳሜ ይደረሳል:: በዚህ መልክ ካላለቀ በዘር/በትውልድ ላይ ችግር ሊያስከትል የሚችል ቅርኘ/ነ፣ ቅሪት ይኖራል ተብሎ ይታመናል:: ሥርዓቱን ተከትሎ ጉዳዩ በወግ ካላለቀ «ቅርኘ/ነ ጀፓሪ» ይባላል:: በመላ ቤተ-ጉራጌ በይፋ ጉራጌ አውቆ የሰየመው አንድ ወግ ብቻ አለ:: ትውልዱና ነዋሪነቱ ኜታ ክፍለ-ሕዝብ ውስጥ ነው::

27. ጩቀማ፣
ጥቆማ

28. መሮ፣
ጠበቃ

29. ሄቶ/ዛር፣ –
ምስክር





30. ጥረ ኦዶት/አውዶት
በሐሰት መመስከር፣ሐሰትን መመስከር

31. ዛር ኢሰንት፣
ለምስክርነት የማይበቃ

32. ቴየ፣
መሐላ

33. ጉርዳ፣
ቃል ኪዳን

34. ፊቸት/ኸትም፣
መስዋዕት

35. ኸተራት

የጠርነት፣ ያለመግባባት፣ የግጭት፣ የጭቅጭቅ ወዘተ. በጊዜያዊነት ማስታገሻ/መግቻ/ማቆሚያ ባህላዊ ሥርዓት ነው:: ሁኔታውም ስምምነት ለመፍጠር፣ ምህረት ለማውረድ ጊዜ ይሰጣል::

36. ወኪያ፣

ከብት/ሀብት ያለው ለሌለው ወገን ላም በመስጠት ተቀባዩ ከላም በሚያገኛቸው ወተት ቅቤና ወዘተ. እንዲሁም አዛባ እየተጠቀመ የሚወለዱ ጥጆችን ከባለሀብቱ ጋር በየተራ እየተካፈሉ መተጋገዣና መደጋገፊያ ኢኮኖሚያዊ ሥርዓት ነው:: ከብቶቹ ሲሞቱ ቆዳቸው ለባለሀብቱ ይሰጣል::

37. ወዘም/ወንዘም

በሁለት ወገኖች ስምምነት የጋራ የሆነን ከብት በእኩል ድርሻ እያረቡ መጠቀም

38. ውኬር፣

«የምሽት ሽንጐ»፣ በየምሽቱ/በየማታው ያቅራቢያ ጐረቤቶች በአካባቢው አዛውንት/ሽማግሌ ቤት በመሰባሰብ ስለሥራ፣ አካባቢ፣ አገር፣ ደኅንነት፣ ታሪክ፣ ባህል ወዘተ. የሚወያዩበት/የሚመካከሩበት መድረክ

39. ማዞያ/ቀራት፣

«የሌሊት ዘብ ጥበቃ»፣ ነዋሪው በቡድን ተደራጅቶ ሌሊት በመዘዋወር የአካባቢውን ፀጥታ/ደህንነት ድምፅ በማሰማት ጭምር የሚያስከብርበት የራስ በራስ የደኅንነት መጠበቂያ አደረጃጀትና ተግባር ነው።

40. አንትሮሽት፣
የእናቶች ዓመታዊ በዓል/Mothers Day

41. ነቄ/ሰንቻ፣
በየዓመቱ ለሣምንት የሚከበር የልጃገረዶች በዓል

42. ሣምር፣

በርካታ ልጆች ስምንት ወይም ከዚያ በላይ ለወለዱ እናቶች ከበሬታ በቤተሰብ መዋጮ ተደግሶ የሚከበር በዓል

43. ቁየ፣
የገና ጨዋታ

44. እቴት፣
ንግሥት፣ እጉንደር ንጉሥ/እአዝማች ባለቤት

45. ቅየ፣
የወሰን/የድንበር ድንጋይ

46. ሜራ፣
ደንብ፣ ሕግ፣ ሥነ-ሥርዓት





47. ኧሰት፣
እንሰት

48. ውሳ፣

ቆሎ፣ ተፍቆ የተቀመጠ ወይም የተጋገረ ኧእሰት ተዋፅኦ

49. ጉንደር፣
አምባር

50. ንጉሥ፣
በቁሙ ንጉሥ ሲሆን፣ ሲነበብ ግን ላላ ተደርጐ ነው።

51. ሰውረር፣

ጉድለት ያለበት፤ በመሆኑም ለባህላዊ ኃላፊነት ቦታዎች ብቁ የማይሆን

52. አጥሜጥ፣
ቡላ

53. ጌዝ፣
ወንፌል/ተራ

54. ኦዜ/አዛይ፣
አራንሺ፣ ቡዳ

55. አቢያ ፣
ወኪል

56. ቢኼ፣
ልቅሶ

57. ኧጭኝ/ን ደረት፣
የአራስ ጥሪ

58. እጀቦች፣

በበዓል ማግስት በተለይ በመስቀርና አረፋ ልጆች ሻኛ ይዘው በመሄድ ወላጆቻቸውን የሚጠይቁበት የከበሬታ ምልክት ሥርዓት

59. ቅርኝ/ነ፣

በቤተሰብ፣ በዘመድ ላይ ችግር እንዳይደርስ መፈጸም ወይም መታሰብ ያለበት ከትውልድ ተያይዞ የሚመጣ ቅሪት፣ ልምድ

60. ጂፐ፣
ከቁጠማና በቀጭኑ ከተገመደ ቃጫ ወይም ከወፊቶና ከቃጫ የሚሠራ ኬሻ/ምንጣፍ

61. ጥብ፣
ጉሣ

62. ዱአ፣
ፀሎት፣ ለአላኽ የሚቀርብ ልመና፣ ምልጃ

63. ሥርጥ እኽርኺ፣
ባልና ሚስት ሲፋቱ ባልየው በፍቺው መስማማቱን ለመግለጽ የሚጠቀምበት ሐረግ ነው፡፡ «ፈትቼሻለሁ፤ ሌላ ትዳር ልትመሠርቺ ትችያለሽ፣ ይቅናሽ፣ ደህና ሁኚ፤ እንደማለት ይመስላል፡፡»

64. በርቾ፣
በሌሎች ላይ የደረሰ መልካም ወይም መጥፎ አጋጣሚ «በርቾ በራር» ሲል፣ አያድርስ ማለት ነው፡፡

65. አንቅ፣
ፍትሕ

66. ወካሽ
ኮረሪማ





67. አግኖት፣
ሠርግ፣ ወግ ማዕረግ

68. ኧቱም ቢኼ፣

እንደ ሟች፣ ዕድሜ፣ ማዕረግ፣ ሥራ፣ ደግነት፣ ጀግንነት፣ ሙያ ወዘተ. ሰዎች በቡድን ሆነው ቆመውና እየተዘዋወሩ በማዜም፣ ከበሮ በመምታት የሟችን የክብር ልብሶች፣ መሣሪያ ወዘተ. በመያዝ ስለፈፀማቸው መልካም ተግባራት በግጥም በማውጣት የሚካሄድ የልቅሶ ሥርዓት

69. ገኝ/ነ፣
አገር

70. ወየግ፣

ሰዎች በመቀባበልና በተራ የሚጫወቱት ባህላዊ «ዘፈን» አልፎ አልፎ ለወገን ማሞገሻ፣ ከሌሎች ጋር እያነፃፀሩ የትልቅነት መግለጫ፣ ከሌላው የራስን ወገን ክብር ከፍ አድርጎ ማሳያነትም ያገለግላል፡፡ ታሪክን ከትውልድ ወደ ትውልድ ማስተላለፊያ ዘዴ ነው፡፡

71. በድራ፣

ለአማልክት (በተለይም ለባህላዊ አማልክት) መለመኛ፣ መማጠኛ፣ ማመስገኛ ወዘተ. በዜማና በቀረርቶ መልክ የሚቀርብ ዝማሬ ወይም ፍካሬ

72. ጀፐረ፣
ጨረሰ/አጠናቀቀ

73. በየ፣

ብልሃት፣ ሥልት («ደም ይጀፑርኳ በየ») ሲል ግድያ ቢፈጸም ደሙ በርቾ/ጡር ሆኖ እንዳይቀጥል የደሙን ጣጣ መጨረሻ/ዕልባት መስጫ ሥልት ወይም ብልሃት ማለት ነው፡፡

74. ነቀረ፣
ነቀለ፣ «ነቆራ» ሲል ተነቀለ ወይም ተነቅሎ ማለት ነው::

75. ሠፐረ፣
ሰበረ

76. ሣምቧ፣
ሣምባ

77. ፈቅ፣
ፍየል

78. እንጣር፣
በትር/ዱላ

79. ዘንጋ፣
ነገር፣ ጉዳይ

80. አመ፣
ሰጠ፣ «ናምኹ ወይ?» ልስጣችሁ?

81. ቂጥየ፣
ቀጥተኛ፣ ቀና፣ ትክክል፣ እውነት፣ ሃቅ

82. አሸ፣
አየ፣ «ታዘውንዩ» ሲል ልታዩልኝ፣ ልትዳኙኝ ወዘተ. ማለት ነው::

83. አኹዋ፣
እርስዎ፣ «ባኹዋ» ሲል በእርስዎ ወይም በእናንተ እንደማለት ነው::

84. ገፓ፣
ገባ፣ «ንግባ» ሲል ልግባ ማለት ይሆናል::





85. ዳኘ/ነ፣
ዳኛ

86. ሙራ፣
ሙሉ፣ ዓመት በዓል

87. ሰቀረ፣
ሰቀለ

88. ንፑዋር፣
በአንዳንድ ወገኖች፣ ለዋቅ፣ ለቦዠ ክብር የሚፈጸም ባህላዊ በዓል

89. ቤደር፣
በጉራጌ ቤት መዝጊያ ራስጌ በሩ ላይ ያለ አንዳንድ ነገሮችን ለማስቀመጥ የሚረዳ ሥፍራ/ቦታ ነው:: «ጡር» ወደ አንድ ቤተሰብ ውስጥ ከመግባቱ ወይም ከመውጣቱ በፊት የቤተሰቡን ሐቀኝነትንና ኢሐቀኝነትን «ለማጣራት» ቤደር ላይ ይቀመጣል የሚል እምነት አለ:: በመሆኑም አንድ ለኅብረተሰቡ ሥርዓት አልዳኝ ያለ ሰው «ቼወ» ሲገባበት አሁንም ለባህሉ አልገዛም ካለ በእምቡተኛው ቤት ከብት ታርዶ ይበላና ሽማግሌዎች «ቤደሩን» ነቅለው ይወጣሉ:: እርግማን የወረደበት በመሆኑ ቤተሰቡን መልካሙ ነገር ሁሉ/ጡር ይርቀዋል ተብሎ ይገመታል::

90. ጡር፣
መልካም ነገር፣ ጥሩ ዕድል

91. ቦገር፣
መብረቅ፣ «ኤቾሁ!!»

92. መንጠ፣
ገፈፈ

93. መስቀር፣
መስቀል፣ የመስቀል በዓል

94. <u>አረፋ፣</u>

ኢድ አል አድሐ

95. <u>ጉራጊና፣</u>

ጉራጊኛ

96. <u>እጉርዳ ዳኘ/ነ፣</u>

የቃል ኪዳን ዳኛ

97. <u>ፈንገያ፣</u>

ሌባ

98. <u>እቒጫ ዳኘ/ነ፣</u>

የሕግ፣ የደንብ፣ የሥነ-ሥርዓት ዳኛ

99. <u>በዋጋ ጡር አውጦት፣</u>

ገንዘብን ማባከን፣.በገንዘብ ግፍ መሥራት

100. <u>ሙራ ገኘ/ነ፣</u>

መላ አገር፣ አካባቢ



## ዋቢ. ሰነዶች


የኢፌዲሪ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት፣ (ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ፣ የኢፌዲሪ ኘሬዚዳንት)፣ <u>የኢትዮጵያ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ ሕገ-መንግሥት፣</u> አዋጅ ቁጥር 1/1987፣ አዲስ አበባ፣ ነሐሴ 15 ቀን 1987 ዓ.ም.

ብሔራዊ ሸንጎ፣ (መንግሥቱ ኃይለማርያም፣ የኢሕዲሪ ፕሬዚደንት)፣ <u>የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሕገ-መንግሥት፣</u> አዲስ አበባ፣ መስከረም 1 ቀን 1980፣

ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ፣ <u>የኢትዮጵያ ሕገ-መንግሥት፣</u> ብርሃንና ሰላም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ማተሚያ ቤት፣ አዲስ አበባ፣ ጥቅምት 24 ቀን 1948 ዓ.ም.

ጉሕራልድ፣<u>የጉራጌ ሕዝብ ራስ-አገዝ ልማት ድርጅት መተዳደሪያ ደንብ፣</u> ቁጥር ጉሕራልድ 001/1980፣ የትምህርት መሣሪዎች ማምረቻና ማከፋፈያ ድርጅት ማተሚያ ቤት፣ አዲስ አበባ፣ 1987 ዓ.ም.

የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት/ጉመሥድ፣ <u>የጉራጌ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ አጥኚና አማካሪ ግብረኃይል፣</u> (ብገር)፤ ቁጥር ጉመሥድ 004/83፣ አዲስ አበባ፣ ግንቦት 1983 ዓ.ም.

The Guraghe Exhibition Committee, <u>**The Guraghes and Their Social Life,**</u> Addis Ababa, 1955.

ገብረየሱስ ኃይለማርያም፣ የኅብረት እንቅስቃሴ፣ "Co-operative Movement", አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት፣ አዲስ አበባ፣ 1965 ዓ.ም.

ሰይፉ ድባቤ፣ አዝማች፣ (የጉራጌ ሕዝብ አጭር ታሪክ)፣ተስፋ ገብረሥላሴ ማተሚያ ቤት፣ አዲስ አበባ፣ ሐምሌ 2 ቀን 1966 ዓ.ም.

የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት፣ የእናት አገር ጥሪ በዓል በሰባት ቤት ጉራጌ፣ የጉልማሶች ትምህርት መምሪያ ማባዣ ዘርፍ፣ (ብገር)፣ አዲስ አበባ፣ ግንቦት 1970 ዓ.ም.

ወልደሥላሴ በረካ (ሌ/ጀኔራል)፣ የኅብረት ሥራ ውጤት፣ ንግድ ማተሚያ ድርጅት (በጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት የታተመ)፣ አዲስ አበባ፣ 1979 ዓ.ም.

ጉመሥድ፣ የኤኮኖሚ ልማትና የአገልግሎቶች ግንባታ መንደርደሪያ ጥናት፣ (ብገር)፣ አዲስ አበባ ታኅሣሥ 1980 ዓ.ም.

ጉመሥድ፣ የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት፣ (ለ25ኛው ዓመት የብር ኢዮቤልዩ መታሰቢያ የተዘጋጀ)፣ የተባበሩት አታሚዎች፣ አዲስ አበባ፣ ጥር 21 ቀን 1980

አብርሃም ሁሴን (ዶ/ር)፣ እና ሀብታሙ ወንድሙ (ዶ/ር) በሥልጢኛ ቋንቋ ተናጋሪ ሕዝብ የአዘርነት በርበሬ ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ፣ ቦሌ ማተሚያ ድርጅት አዲስ አበባ፣ የካቲት 1981

ይርጋ ገብሬ ድሪታ (አዝማች)፣ የጉመሥድ አመሠራረት፣ የሥራ እንቅስቃሴና የወደፊት አዝማሚያ





ማመላከቻዎች፣ (ብገር)፣ ጉመሥድ 002/82፣ አዲስ አበባ፣ መስከረም 1982

ይርጋ ገብሬ ድሪታ (አዝማች) የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት የዕድገት ሂደት፣ (ብገር)፣ጉመሥድ 005/83፣አዲስ አበባ፣ ሐምሌ 1983

ጉመሥድ/ጉሕራልድ፣ የጉራጌ መንገዶች ሥራ ድርጅት 30ኛ ዓመት ክብረ-በዓል፣ አዲስ አበባ፣ ግንቦት 1985 ዓ.ም.

እነድንበሩ ዓለሙ፣ ጎጎት (የጉራጌ ብሔረሰብ ታሪክ)፣ አርቲስቲክ ማተሚያ ድርጅት፣ ወልቂጤ፣ 1987 ዓ.ም.

ተስፋ ገብረየስ ዘምድረ ከብድ (ደራሲ)፣ ወርቁ ተስፋ (አዘጋጅ)፣ አይመለል - ያጉራጌ (የሶዶ ጉርደና) ሕዝብ አጭር የታሪክ ማስታወሻ፣ ንግድ ማተሚያ ድርጅት፣ አዲስ አበባ፣ ግንቦት 1987 ዓ.ም.

ኢ.ህአዴግ፣ የኢ.ህአዴግ፣ የልማት፣ የሰላምና ዴሞክራሲ መርሀ-ግብር፣ አዲስ አበባ፣1987

የደቡብ ብሔር፣ ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ክልላዊ መንግሥት፣ የአምስት ዓመት የልማት፣ የሰምና የዲሞክራሲ መርሀ-ግብር፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ድርጅት፣ አዋሣ፣ ግንቦት 15/1988

ማርቲን ቤርናል (ፕሮፌሰር)፣ ጉራግኛ የግዕዝ አያት ነው፣ እፎይታ 5ኛ ዓመት ቁጥር 10፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ድርጅት፣ አዲስ አበባ፣ ሐምሌ 1989

